# ኤርትራ፡ኩሪ ፩

ዕድሜ ፡ ለተፈሪ ።



አበባዬ ፡ ፍቅሬ ።

ገጽ ፡ ፹፬ ፡ ተመልከት ።

ይህ ፡ መጽሐፍ ፡ ዋናው ፡ ዓላማው ፡ ኢትዮጵያ ፡ ኤርትራን ፡ ላገኘችበት ፡ ቀን ፡ መታሰቢያ ፡ እንዲሆን ፡ ነው ።

ተጻፈ ።

ከም ፡ ፲ ፡ አለቃ ፡ አሸቴ ፡ ደምሴ ።

የጦር ፡ ሠራዊት ፡ ባልደረባ ።

አዲስ ፡ አበባ ፡ ፲፱፻፵፱ ፡ ዓ ፡ ም ፡

በተስፋ ፡ ማተሚያ ፡ ቤት ፡ ታተመ ።

ዋጋው ፡ ፩ ፡ ብር ፡ ከ፶ ፡ ሳንቲም ።

# ኤርትራ ፡ ኩሪ ፤

## ዕድሜ ፡ ለተፈሪ ።



አበባዬ ፡ ፍቅሬ ።

ገጽ ፡ ፳፮ ፡ ተመልከት ።

ይህ ፡ መጽሐፍ ፡ ዋናው ፡ ዓላማው ፡ ኢትዮጵያ ፡ ኤርትራን ፡ ላገኘችበት ፡ ቀን ፡ መታሰቢያ ፡ እንዲሆን ፡ ነው ።

ተጻፈ ።

ከም ፡ ፲ ፡ አለቃ ፡ እሸቴ ፡ ደምሴ ።

የጦር ፡ ሠራዊት ፡ ባልደረባ ።

አዲስ ፡ አበባ ፡ ፲፱፻፵፬ ፡ ዓ ፡ ም ፡

በተስፋ ፡ ማተሚያ ፡ ቤት ፡ ታተመ ።

ዋጋው ፡ ፩ ፡ ብር ፡ ከ፶ ፡ ሳንቲም ።

27.8.62

በሥራው፡ ለደከሙልኝ፡ ለአቶ ፡ ደሳለኝ፡ ሐራ ሚካኤል ፡ ምስጋናዬን ፡ አቀርባለሁ ።

ም ፡ ፲ ፡ አለቃ ፡ እሸቴ ፡ ደምሴ ።



የዚች ፡ ትንሽ ፡ መጽሐፍ ፡ ስም ፡ ኤርትራ ፡ ኩሪ ፡ እድ
ሜ ፡ ለተፈሪ ፡ ይባላል ።

እነዚሁም ፡ የተጻፉት ፡ በመዝሙር ፡ ሲሆን ፡ በዝግታና
በእርጋታ ፡ ለተመለከተው ፡ ምሥጢሩ ፡ በምሳሌ ፡ እየሆነ፡
ብዙ ፡ ነገሮች ፡ ይገኙባቸዋል ፡ ይለቅልኝ ፡ በማለት ፡ በችኰላ
ለሚገሰግሱ ፡ አንባቢዎች ፡ ግን ፡ ምስጢሩ ፡ ምን ፡ እንደሆነ
ለማወቅ ፡ ጥቂት ፡ ያዳግታቸዋልና ፡ በእርጋታ ፡ እንዲያነ
ቡት ፡ አሳስባለሁ ።

መጽሐፉንም፡ ለማሳተም፡ ያሰብኩበት ፡ ምክንያት ፡ እነሆ
ግፈኛው፡ጠላት፡ ሀገራችንን፡ ኢትዮጵያን፡በግፍ፡ ወሯት፡ እኛ
ንም፤ያለ፡ኃዘኔታ፡ በግፍ ፡ ሲቀጠቅጠንና ፡ ሀሰት ፡ የመላበትን፡
ፖለቲካ፡ሲነዛ፡ትምህርት፡ አስተምራለሁ፡እያለ፡ የጭካኔ፡ ሥራ
ውን ፡ ሲያስተምረን፡ቆይቶ፡እንዲሁም፡ የሰውን፡ደም፡ በከንቱ
ከማፍሰስ፡ እንዲወገድ፡ ድል፡ አድራጊው፡ ንጉሠ፡ ነገሥታችን
ቀዳማዊ፡ኃይለ፡ ሥላሴን፡ በሚያስደስት፡ ግርማ፡ ስለመለሰልን
ለቸሩ ፡ አምላካችን ፡ የጋለ፡ ምስጋናችንን ፡ እያቀረብን፡ ከዚያ
ከጭንቅ፡ ወጥተን ፡ ትምህርት ፡ በያይነቱ ፡ እየተማርን፡ ጥበብ
በመገብየት፡ ላይ፡ ሆነን፡ሣለ፡ ዳግም፡ ከብዙ፡ ጊዜ፡ በፊት፡ በባ
ዕድ፡ እጅ፡ ተወስዳ፡ ከባድ፡ ቀምበር፡ ተጭንዋት፡ የነበረችውን
ውዲቱን፡ኤርትራን፡በነፃነት፡ከእናቷ፡ከኢትዮጵያ፡የቀላቀሏት
ን፡ንጉሠ፡ነገሥታችንን፡ ዕድሜ፡ያርዝምልን፡ እያልን፡ የማያቋ
ርጥ፡ጸሎታችንን፡ለልዑል፡እግዚአብሔር፡ ማቅረባችን፡ግልጽ
ሲሆን፡አንዳንድ፡ጊዜም፡ መስሎ፡ የታየንን፡የልባችንን፡ ሐሣብ

በጽሑፍ ፡ ልንገልጸው ፡ የሚገባን ፡ ስለሆነ ፡ እነሆ ፡ እኔም እንዳቅሜ ፡ መስሎ ፡ የታየኝን ፡ የልቤን ፡ አሣብ ፡ የውዲቱን ኤርትሪያን ፡ ከእናት ፡ አገሯ ፡ መቀላቀል ፡ ምክንያት ፡ በማድ ረግ ፡ ከደስታዬ ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፡ ይህችን ፡ ትንሽ ፡ ድርሰት ለክቡራን ፡ አንባቢዎች ፡ ሳቀርብ ፡ በችኰላ ፡ የጻፍኩትን ፡ በእርጋታ ፡ እንድትመለከቱልኝና ፡ እንዲሁም ፡ ይህ ፡ የመ ጀመሪያ ፡ ድርሰቴ ፡ ስለሆነ ፡ አንዳንድ ፡ ያልተባበሩ ፡ ንግግ ሮች ፡ ቢገኙበት ፡ የጐደለውን ፡ ሞልታችሁ ፡ የበዛውን ፡ ቀንሳችሁ ፡ እንድታነቡልኝ ፡ እለምናለሁ ።



ግርማዊ ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡
የኢትዮጵያ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ።



## ግ ር ማ ዊ ፡ ሆ ይ ።

እነሆ ፡ ለምለሟ ፡ ሀገራችን ፡ አምስት ፡ ዓመት ፡ ሙሉ በግፈኛው ፡ ፋሽስት ፡ እጅ ፡ ተወራ ፡ እኛም ፡ በግፍ ፡ ስን ደበደብና ፡ ስንቀጠቀጥ ፡ ቤታችን ፡ ሲቃጠል ፡ ከብታችን፡ ሲታረድ ፡ ዘመዶቻችንም ፡ ቤት ፡ እየተዘጋባቸው ፡ ሲቃ ጠሉ ፡ ይህን ፡ የመሳሰለ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ስቃይ ፡ ስንቀበል ፡ ቆይተን ፡ ድል ፡ አድራጊ ፡ ግርማዊነትዎን ፡ አምላክ ፡ ስላ መጣልን ፡ ያለቁትም ፡ አልቀው ፡ የተረፍነውንም ፡ ከዚያ፡ ጭንቅ ፡ አውጥቶን ፡ ይኸውና ፡ ዛሬ ፡ ነፃነታችንን ፡ ለብሰን በትምህርት ፡ በዕውቀትና ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ጥበብ ፡ እንድን ጐለምስ ፡ የሚያደርጉት ፡ ድካምና ፡ የሚያወጡት ፡ ገንዘብ ብዛቱ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ተብሎ ፡ ለመገመት ፡ የሚያዳግት ፡ ከመ ሆኑም ፡ በላይ ፡ በየጊዜው ፡ በየትምህርት ፡ ቤቶቹ ፡ እየሄዱ ለተማሪዎችና ፡ ላስተማሪዎች ፡ የሚሰጡት ፡ ምክር ፡ ለሰሚ ዎችና ፡ ለተመካሪዎች ፡ እንደ ፡ ጥሩ ፡ ምግብ ፡ ልብ ፡ የሚ ያወፍርና ፡ ወጣት ፡ የሚያጐለምስ ፡ ለሕዝብ ፡ ሁሉ ፡ ሙሉ፡ ተስፋ ፡ በየልቡናው ፡ የሚያሳድር ፡ ሲሆን ፡ በየአውራጃው ና ፡ በየግዛቶቹ ፡ የትምህርት ፡ ቤቶች ፡ አቁመውልን ፡ የሀ ገራችንን ፡ ቋንቋ ፡ ትምህርት ፡ እንድንማር ፡ ከማድረግዎ፡ በላይ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ቋንቋ ፡ ትምህርትና ፡ ልዩ ፡ ልዩ ጥበብ ፡ እንድንማርልዎ ፡ እልፍ ፡ አእላፍ ፡ ወርቅ ፡ እያወጡ አስተማሪ ፡ ቀጥረውልን ፡ ሳለ ፡ ተግቶ ፡ መማርና ፡ ጥበብን ፡ መገብየት ፡ የእኛ ፡ ፈንታ ፡ መሆኑ ፡ አይዘነጋንም ።

ዳግም ፡ ከብዙ ፡ ዓመት ፡ በፊት ፡ ከእናት ፡ አገርዋ ፡ ከኢትዮጵያ ፡ ተለይታ ፡ የነበረችውን ፡ ውዲቱን ፡ ኤርት

ራን ፡ ዛሬ ፡ መልሰው ፡ ስለቀላቀልዋት ፡ ደስታችን ፡ ወሰን ፡ የሌለው ፡ ነው ።

ስለዚህ ፡ ከላይ ፡ የተጠቀሱትን ፡ ውለታዎች ፡ የዋሉልንን ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥታችንን ፡ ዕድሜ ፡ አርዝሞልን ፡ ወደፊትም ፡ ያሰቧቸውን ፡ አሳቦች ፡ ከመልካም ፡ ፍጻሜ ፡ እንዲያደርሱና ሌሎቹንም ፡ በባዕድ ፡ እጅ ፡ ያሉትን ፡ ጠረፎቻችንን ፡ እንደ ኤርትሪያ ፡ መልሰው ፡ ከእናት ፡ አገራቸው ፡ ከኢትዮጵያ ፡ እንዲያቀላቅሉዋቸውና ፡ ከመከራ ፡ ቀምበር ፡ እንዲያወጡ አቸው ፡ ሺህ ፡ ዓመት ፡ ያንግሥዎት ፡ እያልን ፡ እያንዳንዳችን ኢትዮጵያዊ ፡ ሁሉ ፡ የማያቋርጥ ፡ ጸሎታችንን ፡ ለልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ ማቅረባችንን ፡ ግርማዊነትዎም ፡ የማይዘነ ጋው ፡ ሲሆን ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ምስጋናዎንና ፡ ታሪክዎን መጻፍ ፡ የእያንዳንዳችን ፡ አገልጋይዎችም ፡ ተግባር ፡ ስለሆነ እኔም ፡ ይህችን ፡ አነስተኛ ፡ መጽሐፍ ፡ ሳይረዝም ፡ በጭሩ ሳይበዛ ፡ በጥቂቱ ፡ አሳትሜ ፡ ለግርማዊነትዎ ፡ ሳበረክት ፡ በታ ላቅ ፡ ትሕትና ፡ ነው ።

ወጣት ፡ አገልጋይዎ ፡ ም | የ፲ ፡ አለቃ ፡ እሸቴ ፡ ደምሴ ።





ጠቅል ፤ ኤርትራ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ነፍስ ፡ ጡር ፡ ነበርሽ ፡
ይመስገን ፡ ፈጣሪ ፡ ነፃነት ፡ ወለድሽ ፡
እመቤቴ ፡ ማርያም ፡ እንኳን ፡ ማረችሽ ፡
እናትሽ ፡ ኢትዮጵያ ፡ የምታርስሽ ፡
አረንጓዴ ፡ ብጫ ፡ ቀይ ፡ ሐር ፡ አልብሳሽ ፡
በጠቅል ፡ ዘውድ ፡ ሥር ፡ ለብሰሽ ፡ ተምነሽነሽ
ይገባሻልና ፡ ስለአራስ ፡ ጥሪሽ ፡
መነን ፡ ጥበብ ፡ ኩታ ፡ ያውልሽ ፡ ልበሽ ፡
ኤርትራ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፡ ይብዛ ፡ ደስታሽ ፡
ተቀመጭ ፡ ባልጋ ፡ ላይ ፡ ከእኔ ፡ ቤት ፡ ገብተሽ
አይዞሽ ፡ አታስቢ ፡ እኔ ፡ አለሁልሽ ።
እንኳንስ ፡ ላንችና ፡ ለራሴ ፡ ወጣት ፡
ለሰው ፡ እበጃለሁ ፡ እኔ ፡ ያንች ፡ አባት ፡
እንግዲህ ፡ በነፃ ፡ ያላንዳች ፡ ሥጋት ፡
ኑሪ ፡ ለዘለዓለም ፡ ሆነሽ ፡ መሠረት ።

ኤርትራ ፤ ጠቅል ፡ የኔ ፡ ጌታ ፡ መጣሁ ፡ እኔ ፡ አገርህ ፡
እግዚአብሔር ፡ ይመስገን ፡ ገብቻለሁ ፡ እጅህ ።
እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ተጠምጄ ፡ ነበር ፡
ባልተለበለበ ፡ በመከራ ፡ ቀንበር ።
ከመከራ ፡ ወጣሁ ፡ ዕድሜ ፡ ለተፈሪ ፡
ግዛኝ ፡ ለዘለዓለም ፡ ታጠቅ ፡ ድርብ ፡ ሱሪ ።
በያይነቱ ፡ ጥበብ ፡ ብዙ ፡ ኩታ ፡ አለኝ ፡
ጠቅለህ ፡ በድምር ፡ ተፈሪ ፡ ግዛኝ ።
ከሌላ ፡ ከመኖር ፡ ደልቶኝ ፡ በጌትነት ፡
እመርጣለሁ ፡ በጣም ፡ ካንተ ፡ ጋር ፡ ድህነት ፡
ዳሩስ ፡ ምን ፡ ጠፉና ፡ ከጠቅል ፡ ቤት ፡
የሚገኘው ፡ ጥበብ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ዓይነት ፡
ብዙ ፡ እምቦቀቅላ ፡ ሚሊዮን ፡ ወጣት ፡
ጠዋትና ፡ ማታ ፡ የሚፈልቅበት ፡

መልካሚቱ ፡ እናቴ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ናት ፡
ቸሩ ፡ መድኃኔ ፡ ዓለም ፡ በጣም ፡ ጠብቃት ፡
አደራ ፡ ጌታዬ ፡ ክፉ ፡ አታስነካት ፡
በጣም ፡ አጥባቂ ፡ ነኝ ፡ ዘወትር ፡ ጸሎት ፡
ውዲቱ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ቅድስት ፡ የእኔ ፡ እናት ፡
በክፉ ፡ የሚያይሽ ፡ ጨካኙ ፡ ጠላት ፡
አፈር ፡ ሆኖ ፡ ቀረ ፡ ገባ ፡ ከመሬት ።
ቢመካ ፡ በጉልበት ፡ በብዙ ፡ መሣሪያ ፡
አንቺ ፡ ድል ፡ ነሣሽው ፡ ከጸሎትሽ ፡ ጋራ ።
ከጠላት ፡ መሣሪያ ፡ ከብዙ ፡ ጉልበት ፡
ትበልጣለች ፡ ያንቺ ፡ ትንሽዋ ፡ ጸሎት ።

ኢትዮጵያ ፤ ሰላም ፡ ላንቺ ፡ ይሁን ፡ ኤርትራ ፡ ልጄ ፤ ሆይ ፡
እንደምን ፡ ከርመሻል ፡ በደህና ፤ መጣሽ ፡ ወይ ።

ኤርትራ ፤ አዎን ፡ ደህና ፡ መጣሁ ፡ መልካሚቱ ፡ እናቴ ፡
ዕድሜ ፡ ለተፈሪ ፡ ለጀግናው ፡ አባቴ ።

ኢትዮጵያ ፤ አንቺም ፡ ስትናፍቂኝ ፡ እኔም ፡ ስናፍቅሽ ፡
እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ነበር ፡ ስጠብቅሽ ፡
ነይ ፡ ጠጋ ፡ በይና ፡ አጥብቄ ፡ ልይሽ ፡
ከደረቴ ፡ አቅፌ ፡ ስሜ ፡ ልጥገብሽ ፡
ተመልሶ ፡ መጥቶ ፡ ጠቅል ፡ አባትሽ ፡
እኔን ፡ አገኘና ፡ አንችን ፡ ስላጣሽ ፡
በናፍቆት ፡ ነበረ ፡ ሲጠባበቅሽ ፡
አሁን ፡ ደስ ፡ ብሎታል ፡ መጥተሽ ፡ ስላየሽ ፡
ከመከራ ፡ ቀምበር ፡ አምላክ ፡ ካወጣሽ ፡
በጠቅል ፡ ብርታት ፡ ለዚህ ፡ ከበቃሽ ፡
እኔን ፡ ደስ ፡ ብሎኛል ፡ እንኳን ፡ ደስ ፡ ያለሽ ፡
ሊባል ፡ ያስደፍራል ፡ ሞተሽ ፡ ተነሣሽ
ከመቃብር ፡ አፈር ፡ ከጉድጓድ ፡ ወጣሽ ፡

እንግዲህ ፡ ግድ ፡ የለም ፡ አያስብ ፡ ልብሽ ፡
የሚነካሽ ፡ የለም ፡ በእጇ ፡ ከገባሽ ።
ኤርትራ ፤ ዕድሜ ፡ ለተፈሪ ፡ ገባሁኝ ፡ ከቤቴ ፡
ተለይቼ ፡ ስኖር ፡ ከመልካሟ ፡ እናቴ ፡
ገና ፡ ትንሽ ፡ ሆኜ ፡ በሕፃንነቴ ።
እናቴ ፡ ኢትዮጵያ ፡ አለሽልኝ ፡ ወይ ፡
ውዲቱ ፡ ደጊቱ ፡ አበባዬ ፡ ሆይ ፡
ሳልበላ ፡ እጠግባለሁ ፡ አንችን ፡ አንችን ፡ ሳይ
ለምለሟ ፡ እመቤቴ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ሆይ ።
ጥንትም ፡ ክርክሩ ፡ በከንቱ ፡ ነው ፡ እንጅ ፡
እንዴት ፡ ትለያለች ፡ ከእናት ፡ ሕፃን ፡ ልጅ ።
ይገርማል ፡ በብርቱ ፡ ይደንቃል ፡ በጣም ፡
ከእንግዲህስ ፡ ወዲያ ፡ ከእጅሽ ፤ አልወጣም ።
ለልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡ጸሎት ፡ አቀርባለሁ ፡
ከውድ ፡ እናቴ ፡ ጋር ፡ ተገናኝቼአለሁ ፡
አንበሳውን ፡ ንጉሥ ፡ ጠቅልን ፡ ይዣለሁ ፡
ቁመቴም ፡ ይረዝማል ፡ እንግዲህ ፡ አድጋለሁ ።
እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ታስሬ ፡ በገመድ ፡
ዓይኔ ፡ ሲንከራተት ፡ ሲናፍቀኝ ፡ ዘመድ ።
መጣሁ ፡ እኔ ፡ ልጅሽ ፡ ገመዱን ፡ በጥሼ ፡
ሌት ፡ ከቀን ፡ ሳልተኛ ፡ በፍጥነት ፡ ገስግሼ ፡
እንግዲህ ፡ ልሳምሽ ፡ መልሼ ፡ መልሼ ።
አይዞሽ ፡ ኢትዮጵያ ፡ መጣሁ ፡ እኔ ፡ ልጅሽ ፡
እንግዲህ ፡ እቀፊኝ ፡ ገብቻለሁ ፡ ከጅሽ ።
የበዛ ፡ ምስጋና ፡ ለጠቅል ፡ ይሁን ፡
በስንት ፡ ዓመታችን ፡ ዛሬ ፡ አገናኘን ፡
ይመስገን ፡ ፈጣሪ ፡ እሱን ፡ የሰጠን ፡
የነፍሳችን ፡ ጌታ ፡ የሕይወታችን ፡

አንበሳው ፡ ተፈሪ ፡ ውድ ፡ ጌታችን ፡
ባለም ፡ አላየሁም ፡ የሚያህል ፡ እሱን ።
አምላክ ፡ ይጠብቀው ፡ በሰማይ ፡ በምድር ፡
አያልቅም ፡ ተጽፎ ፡ የሠራው ፡ ታምር ።
ኢትዮጵያ ፤ መቸም ፡ አያልቅበት ፡ ቅዱስ ፡ መለኮት ፡
ኤርትራን ፡ ከኔ ፡ ጋር ፡ አቀላቀላት ፡
ማድረግ ፡ ይገባኛል ፡ ዘወትር ፡ ጸሎት ።
ሕዝብ ፤ እሰይ ፡ የምሥራች ፡ ኤርትራ ፡ መጣች ፡
ከውዲቱ ፡ እናቷ ፡ ተቀላቀለች ።
እስከ ፡ ዛሬ ፡ ስትኖር ፡ እየናፈቀች ፡
ወይ፡እናት፡ወይ፡አባት ፡ ወይ፡እኅት ፡ እያለች ፤
ይኸው ፡ ዛሬ ፡ መጣች ፡ ከአገርዋ ፡ ገባች ።
ኢትዮጵያ ፡ እናታችን ፡ እንኳን ፤ ደስ ፡ ያለሽ ፡
ስለመጣችልሽ ፡ ውዲቱ ፡ ልጅሽ ።
ጠቅልም ፡ ጌታችን ፡ እንኳን ፡ ደስ ፡ ያለህ ፡
የታሰበው ፡ ሁሉ ፡ ተፈጸመልህ ።
በያይነቱ ፡ ምግብ ፡ ሞልቶ ፡ ከቤትህ ፡
ዘወትር ፡ ዳዊት ፡ ነው ፡ ምሣና ፡ እራትህ ።
ከሃምሣ ፡ ዓመት ፡ በፊት ፡ የተዘጋው ፡ በር ፤
ተከፈተ ፡ ዛሬ ፡ ዕድሜ ፡ ለጠቅል ።
ተዘግቶ ፡ የነበር ፡ ውሉ ፡ ጭላንጭሉ ፤
ዕድሜ ፡ ለተፈሪ ፡ ተከፈተ ፡ በሩ ።
በአሥራ ፡ ዘጠኝ ፡ መቶ ፡ ሠላሳ ፡ ሦስት ፡
ለምለሟን ፡ ኢትዮጵያን ፡ ከጭንቅ ፤ አዳንካት
ይኸው ፡ ደግሞ ፡ ዛሬ ፡ በያዝነው ፤ ዓመት ፡
ውዲቱ ፡ ኤርትራን ፡ ነፃ ፡ አወጣሃት ፡
ተፈሪ ፡ አባ ፡ ጠቅል ፡ ያንተ ፡ ታምራት ፡
በጣም ፡ ያስገርማል ፡ ይደንቃል ፡ በውነት ፡

ጠላትን ፡ ድል ፡ አድራጊ ፡ ገዳይ ፡ በጸሎት ፡
ፍቅርህ ፡ የሚጣፍጥ ፡ ከማር ፡ ከወተት ፡
የሕዝብ ፡ ተስፋ ፡ ነህ ፡ የብዙ ፡ ወጣት ፡
አማቢ ፡ ለሀገር ፡ ማታና ፡ ጠዋት ፡
አንበሳችን ፡ ጠቅል ፡ የእኛ ፡ እናት ፡ አባት ፡
የሠራህ ፡ ነህና ፡ ብዙ ፡ ጀግንነት ፡
መሥራት ፡ ይገባናል ፡ ካለህ ፡ በሕይወት ።
ላንተ ፡ መታሰቢያ ፡ የወርቅ ፡ ሐውልት ፡
ሁላችን ፡ ተባብረን ፡ ሆነን ፡ ባንድነት ።
ተከራካሪ ፡ ነው ፡ ፍርድ ፡ አስተካካይ ፡
አንበሳው ፡ ተፈሪ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ፀሐይ ።
ለምለሟ ፡ ኤርትራ ፡ እንኳን ፡ ደስ ፡ ያለሽ ፤
በመቀላቀልሽ ፡ ከውድ ፡ እናትሽ ፡
አረንጓዴ ፡ ብጫ ፡ ቀይ ፡ ሐር ፡ ኩታሽ ፡
ጥበብ ፡ ነፃነት ፡ ነው ፡ ደግሞ ፡ ቀሚስሽ ፡
ምስጋና ፡ አቅርቢለት ፡ በውነት ፡ ከሆድሽ ፤
ለኀይለ ፡ ሥላሴ ፡ ነፃ ፡ ላወጣሽ ።
፲፱ዶቹ ፡ አውራጃዎቻችን ፡
እሰይ ፡ የምስራች ፡ መጣች ፡ እኅታችን ፡
ተለይታ ፡ ስትኖር ፡ ከመካከላችን ።
በጣም ፡ በዝቶ ፡ ነበር ፡ እኛም ፤ ናፍቆታችን ፤
እንግዲህ ፡ ከመጣች ፡ ካየናት ፡ ባይናችን ፡
ይመስገን ፡ ፈጣሪ ፡ ይብዛ ፡ ደስታችን ።
ውዲቱ ፡ ኢትዮጵያ ፡ እናታችን ፡ ሆይ ፡
እንዴት ፡ ትደሰቺ ፡ ኤርትራን ፡ ስታይ ።
ከብዙ ፡ ዓመት ፡ በፊት ፡ ካንች ፡ ተነጥላ ፡
ስትቀበል ፡ ኑራ ፡ አያሌ ፡ መከራ ።
ተመስገን ፡ እግዚአብሔር ፡ ቸሩ ፡ ፈጣሪያችን ፡

ዘለዓለም ፡ አኑረን ፡ በነፃነታችን ፡
ማመስገን ፡ ይገባል ፡ ዘለዓለም ፡ አንተን ፡
ለምለሚን ፡ ኤርትራን ፡ አመጣህልን ፡
ከውድ ፡ እናታችን ፡ ቀላቀልክልን ፡
በጣም ፡ ጠብቅልን ፡ ንጉሣችንን ፡
ውድ ፡ አባታችንን ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴን ፡
ነፍስዎን ፡ ይማረው ፡ ራስ ፡ መኰንን ፡
ለኢትዮጵያ ፡ ፀሐይ ፡ ያፈለቁልን ፤
እንዲህ ፡ መኖራችን ፡ ነፃነት ፡ ለብሰን ፤
እሱን ፡ ቢሰጠን ፡ ነው ፡ ቸሩ ፡ አምላካችን ፡
የአስፋው ፡ ወሰን ፡ አባት ፡ የነመኰንን ፡
አንተን ፤ ያኑርልን ፡ ለባንዲራችን ፡
ጥበብ ፡ እንዲማሩ ፡ ወጣቶቻችን ፤
እንድንተባበር ፡ እኛ ፡ ሁላችን ፡
አረንጓዴ ፡ ብጫ ፡ ቀይ ፡ ሐር ፡ ለብሰን ፡
ምኞታችን ፡ ሁሉ ፡ እያንዳንዳችን ፡
ጠቅል ፡ ያንተን ፡ ዕድሜ ፡ እንዲያረዝምልን ፡
ዘላለም ፡ አይጠፋም ፡ ከልበናችን ፡
በባዕድ ፡ እጅ ፡ ያሉት ፡ ጠረፎቻችን ፡
እንዲቀላቀሉ ፡ ከመሐላችን ።

ጠቅል ፤ እሺ፡የእኔ ልጆች ተባበሩ፡እናንተ ነፃነት ልበሱ
አሁን ፡ ይመጣሉ ፡ አይቀሩም ፡ እነሱ ፡
ያውም ፡ በችኰላ ፡ እየገሰገሱ ፡
አረንጓዴ ፡ ብጫ ፡ ቀይ ፡ ሐር ፡ ሊለብሱ ።

ኤርትራ ፤ አሥራ ፡ ሁለቶቹ ፡ የእኔ ፡ ወንድሞች ፡
ያንበሳው ፡ ተፈሪ ፡ የጠቅል ፡ ልጆች ፡
ለምለም ፡ አበባዎች ፡ ወጣት ፡ ወጣቶች ።
እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ከተለያየን ፡

እንደምን ፡ አላችሁ ፡ በጣም ፡ ብዙ ውን ።
ለእኔ ፡ ስታስቡ ፡ በብዙው ፡ አዝናችሁ ፡
ቸሩ ፡ መድኃኔ ፡ ዓለም ፡ መልካም፡ አሳያችሁ፡
ተቀላቅያለሁ ፡ ከመካከላችሁ ።
አምላክን ፡ በብርቱ ፡ አመሰግናለሁ ፡
ከውድ ፡ እናቴ ፡ ጋር ፡ ተቀላቅያለሁ ፡
አረንጓዴ ፡ ብጫ ፡ ቀሚስ ፡ ለብሻለሁ ፡
እንግዲህ ፡ በነፃ ፡ ኰርቼ ፡ እኖራለሁ ፡
ዕድሜ ፡ ለተፈሪ ፡ ማንን ፡ እፈራለሁ ።

ደራሲ ። ከተፈጸመልኝ ፡ ተስፋና ፡ ሐሳቤ ፡
ኰርቼ ፡ እኖራለሁ ፡ ከነቤተ ፡ ሰቤ ።
ያንን ፡ ሁሉ ፡ ጭንቀት ፡ ጥዬ ፡ ከመሬት ፡
ለብሼ ፡ መኖሬ ፡ ሙሉ ፡ ነፃነት ፡
አንተን ፡ ቢሰጠኝ ፡ ነው ፡ ቅዱስ፡ መለኮት ።
ሕመምተኛም ፡ ዳነ ፡ እልል ፡ እንበል ፡
ኤጀርሳ ፡ ጎሮ ፡ ላይ ፡ ፈለቀ ፡ ጠበል ።
ኤጀርሳ ፡ ጎሮ ፡ ላይ ፡ ይተከል ፡ ሀውልት ፡
ለኢትዮጵያ ፡ ብርሃን ፡ ፀሐይ ፡ የወጣበት ።
እንዳንተ ፡ አላየሁም ፡ የንጉሥ ፡ ረቂቅ ፡
ጠዋትና ፡ ማታ ፡ ቀን ፡ የምትናፍቅ ፡
ከአልማዝ ፡ የምትበልጥ ፡ ከነጠረው ፡ ወርቅ ።
በሐምሌ ፡ ተወልዶ ፡ በጥቅምት ፡ የነገሠው ፡
እንደሱ ፡ አላየሁም ፡ ባለም ፡ ተፈሪ ፡ ሰው ፡
ቸሩ፡ መድኃኔ፡ ዓለም፡ሺ ሀ፡ዓመት፡ ያንግሠው ።
ሳይርበኝ ፡ መብላቴ ፡ ሳይበርደኝ ፡ መልበሴ ፡
በነፃነቴ ፡ ነው ፡ በኃይለ ፡ ሥላሴ ።
በዓለም ፡ መንግሥታቶች ፡ ተሰምቷል፡ ዝናህ፡
ዕድሜህን ፡ ያርዝመው ፡ ልዑል ፡ አምላክህ ።

ፅድሜህ ፡ በጣም ፡ ይርዘም ፡ ተፈሪ ፡ ጌታችን ፡
ከአምላካችን ፡ ጋር ፡ አንተነህ መኩሪያችን ።
ዝሆንም ፡ ነብርም ፡ ጐሽም ፡ ክፉ ፡ አውሬ ፡ ነው ፡
ከሁሉም ፡ አንበሳ ፡ ባለም ፡ ተፈሪ ፡ ነው ።
አሞራ ፡ ልትበላን ፡ ከፍታ ፡ ነበር ፡ አፏን ፡
ተፈሪ ፡ አንበሳችን ፡ ገነጠላት ፡ ክንፏን ።
በዚያ ፡ በክፉ ፡ ቀን ፡ በአምስቱ ፡ ዓመት ፡
ጨልሞብን ፡ ነበር ፡ ቀኑ ፡ እንደ ፡ ሌሊት ፡
ፅድሜ ፡ ለተፈሪ ፡ ወጣን ፡ ከጭንቀት ።
ሶላቶ ፡ ሲረግጠን ፡ ባገራችን ፡ ላይ ፡
ተመስገን ፡ አምላኬ ፡ ወጣን ፡ ከስቃይ ።
ድንገት ፡ የፈለቀው ፡ ከኤጀርሳ ፡ ጎሮ ፡
ከጅብ ፡ አፍ ፡ አወጣን ፡ ከዘንዶ ፡ ጉሮሮ ።
እንዳንት ፡ ያለ ፡ ንጉሥ ፡ የድሀ ፡ ቀኝ ፡ እጅ ፡
ንግግርህ ፡ ጣፋጭ ፡ ከወተት ፡ ከጠጅ ፡
አንተን ፡ ያመነ ፡ ሰው ፡ አይወድቅም ፡ ከደጅ ።
የኢትዮጵያ ፡ ንጉሥ ፡ ላደረገህ ፡ ጌታ ፡
ምስጋና ፡ አቀርባለሁ ፡ ጠዋትና ፡ ማታ ፡
በልቼ ፡ ማደሬ ፡ በሰፌ ፡ ገበታ ፡
አንተን ፡ ቢሰጠኝ ፡ ነው ፡ አምላክ ፡ የኔ ፡ ጌታ ።
እናትና ፡ አባቴን ፡ ትቼ ፡ መጥቻለሁ ፡
እንደቸሩ ፡ እግዚአብሔር ፡ አንተን ፡ አምኛለሁ ።
ካገሬ ፡ ስወጣ ፡ ትቼ ፡ እናት ፡ አባት ፡
ስፈልግ ፡ ነውና ፡ መልካሙን ፡ ትምህርት ፡
ፍለጠኝ ፡ ቁረጠኝ ፡ ግረፈኝ ፡ በውቀት ፡
ግዛኝ ፡ ለዘለዓለም ፡ ንገሥ ፡ ሺህ ፡ ዓመት ፡
ቀኑ ፡ ለምለም ፡ ይሁን ፡ የነገሥክበት ፡
ደግሞም ፡ ኤጀርሳ ፡ ላይ ፡ የፈለቅህበት ፡

ማክበር ፡ ይገባናል ፡ ሳንወጣ ፡ ከቤት ፡
በሱ ፡ ነው ፡ የቆመው ፡ ይኸ ፡ ነፃነት ፡
ይገባናል ፡ ማድረግ ፡ ዘወትር ፡ ጸሎት ፡
ያንግሥህ ፡ ዘለዓለም ፡ ቅዱስ ፡ መለኮት ።
ሺህ ፡ ብር ፡ የሚያወጣ ፡ ጥበብ፡ኩታ፡አለን፡
አንሸጥም ፡ ለሌላ ፡ ተፈሪ ፡ ግዛን ።
ኤጀርሳ ፡ ጎሮ ፡ ላይ ፡ የወጣው ፡ ፀሐይ ፡
የዘለዓለም ፡ ብርሃን ፡ በኢትዮጵያ ፡ ላይ ።
ኢትዮጵያ ፡ አገራችን ፡ የያዝሽው፡ንጉሥ፡
ጠላት ፡ የሚበትን ፡ እንዳውሎ ፡ ነፋስ ፡
ጣልያንን ፡ አረገው፡ያንድ ፡ ሰዓት ፡ ቁርስ ።
ትምህርት ፡ አፍቃሪ፡ነው፡ለዕውቀት፡ተጣጣሪ፡
በሰማይም ፡ ቢሆን ፡ ይማራል ፡ ተፈሪ ።
የጥበብ ፡ ምንጭ ፡ ነው፡የውቀት፡መደብር፡
ተማሪ ፡ ነውና ፡ በሰማይ ፡ በምድር ።
ይመስገን ፡ ፈጣሪ ፡ አንተን ፡ የሰጠን ፡
ጠላትን ፡ በጸሎት ፡ ድል ፡ አድራጊውን ።
በላሌ ፡ መግዛቴ ፡ ማን፡ሊታጠቀው ፡ ነው ፡
እኔ ፡ የምለብሰው ፡ ተፈሪ ፡ ሱሪ ፡ ነው ።
ተፈሪ ፡ ሱሪዬ ፡ እንዳያልቅብኝ ፡
ዘላለም ፡ ካልጋ ፡ ላይ ፡ አይውረድብኝ ።
ዕድሚሽን ፡ ያርዝመው ፡ ቸሩ ፡ ፈጣሪያችን ፡
የመኰንን ፡ እናት ፡ ያልጋ ፡ ወራሻችን ፡
የቀኝ ፡ ዓይናችን ፡ ነሽ ፡ የእኛ ፡ ብርሃናችን ፡
ሺህ ፡ ዓመት ፡ ያኑርልን ፡ ቸሩ ፡ ፈጣሪያችን ።
ቤትህን ፡ ስትሠራ ፡ የሀገሬ ፡ ሰው ፡
አስፋው ፡ ግድግዳውን፡እንዲረዝም፡ዕድሜው
ሁልጊዜ ፡ ገና ፡ ነው ፡ ሁልጊዜ ፡ ዕንቁጣጣሽ፡

ዕድሜ ፡ ለአስፋ ፡ ወሰን ፡ ለደጉ ፡ አልጋ ፡ ወራሽ ።
አንተን ፡ የፈጠረ ፡ ልዑል ፡ አምላካችን ፡
ይመስገን ፡ በብዙ ፡ ቸሩ ፡ ፈጣሪያችን ፡
ዕድሜ ፡ ለመኰንን ፡ ዕድሜ ፡ ለአስፋ ፡ ወሰን ፡
ኰርተን ፡ እንኖራለን ፡ ነፃነትን ፡ ለብሰን ።
በመኰንን ፡ ነበር ፡ ጥንት ፡ የምትገዛው ፡
ሐረር ፡ ዕድለኛ ፡ ዛሬም ፡ አለች ፡ በዚያው ።
የሐረር ፡ ከተማ ፡ ይመር ፡ ዕድልሽ ፡
ዘላለም ፡ መኰንን ፡ የሚኖርብሽ ፡
ምስጋና ፡ አቀርባለሁ ፡ ለደጉ ፡ አምላክሽ ፡
በውነት ፡ አስቦልሽ ፡ እሱን ፡ ለሰጠሽ ።
ደስ ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፡ ስገባ ፡ እቤትህ ፡
አበባ ፡ ታቅፋ ፡ ሳይ ፡ ባለቤትህ ።
እግዚአብሔርም ፡ አይቶ ፡ ያንተን ፡ ደግነት ፡
አበባ ፡ አስታቀፈህ ፡ በወጣትነት ።
የማይወድህ ፡ የለም ፡ የማያፈቅርህ ፡
በሁለቱም ፡ እጅህ ፡ አበባ ፡ ይዘህ ።
ምንኛ ፡ ደግ ፡ ነው ፡ ልዑል ፡ እግዚአብሔር ፡
አንተን ፡ የተከለ ፡ ለሐረር ፡ ደብር ።
በደሴ ፡ በወሎ ፡ አንተ ፡ አስፋ ፡ ወሰን ፡
በሐረር ፡ አውራጃ ፡ ልዑል ፡ መኰንን ።
ግርማዊት ፡ እቴጌ ፡ ስም ፡ ማውጣት ፡ ያውቃሉ ፡
ዳር ፡ እስከ ፡ ዳር ፡ አስፋው ፡ መኰንን ፡ ይላሉ ።
እባክህ ፡ መኰንን ፡ ኩታ ፡ ሥራልኝ ፡
በያይነቱ ፡ ጥበብ ፡ ታውቃለህ ፡ አሉኝ ።
ልዑል ፡ አልጋ ፡ ወራሽ ፡ ኩታ ፡ ይወዳሉ ፡
በጥበብ ፡ ላይ ፡ ጥበብ ፡ ለብሰው ፡ ይውላሉ ።
ልዕልት ፡ ፀሐይም ፡ ውዲቱ ፡ እኅታቸው ፡

ጥበብ ፡ ብቻ ፡ ነበር   በመላው ፡ ልብሳቸው ።
አስቋጥረው ፡ ነበረ ፡ ከሸማኔ ፡ ቤት ፡
ብዙ ፡ ጥበብ ፡ ኩታ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ዓይነት ።
ገንዘቡንም ፡ ከፍለው፡ለብሰው ፡ ሳይጠግቡት ፡
በድንገት ፡ ተነስተው ፡ ሄዱ ፡ ትተውት ።
በጥቅምት ፡ በኅዳር ፡ በትሣሥ ፡ ፀሐይ ፡ ነው
በነሐሴ ፡ መሸና ፡ ጨለመብን ፡ ምነው ።
በጥቅምት ፡ በኅዳር ፡ በትሣሥ ፡ የሞቅሽኝ ፡
ምነው ፡ በነሐሴ ፡ ሆዴን ፡ አቃጠልሽኝ ።
ሐረርም ፡ ጐጃምም ፡ ደሴም ፡ ጅምበር ፡ ወጣች
ምነው ፡ ነቀምቴ ፡ ላይ ፡ ፍጹም ፡ ፀሐይ፡ጠፋች
ፀሐይ ፡ ወጣች ፡ ብለን ፡ ደስ ፡ ደስ ፡ ሲለን
ምነው ፡ በነሐሴ ፡ ጠለቀችብን ።
አንቺ ፡ እቴጌ ፡ መነን ፡ የሕግ ፡ ወርቅሽ ፡
ተናኘ ፡ በብዙ ፡ ሞላ ፡ በጣትሽ ።
ሳላይሽ ፡ ነበረ ፡ ጥንት ፡ ልብሳችን ፡
ዛሬስ ፡ በኢትዮጵያ ፡ ተናኘ ፡ መነን ።
አዲስ ፡ አበባ ፡ ላይ ፡ ዝናብ ፡ ጥሎ ፡ ነበር ፡
በነፋሱ ፡ ብዛት ፡ ተናኘ ፡ እስከ ፡ ጎንደር ።
በረዶ ፡ ነበረ ፡ ያለም ፡ ዝናብ ፡ ሁሉ ፡
በኢትዮጵያ ፡ መሬት ፡ ዘነበ ፡ ወርቅ ፡ አሉ ።
አዲስ ፡ አበባ ፡ ላይ ፡ ትልቅ ፡ ዝናብ ፡ ጥሎ
ምነው ፡ ቸኰለና ፡ አባራ ፡ በቶሎ ።
የኢትዮጵያ ፡ ወታደር ፡ መላው ፡ ሠራዊት
ጠንክረን ፡ እንማር ፡ የጦር ፡ ብልሀት ፡
ሊያጠቃም ፡ ቢመጣ እንዲያፍር ፡ ጠላት ።
ምስጋና ፡ አቀርባለሁ ፡ ላገሬ ፡ ወጣቶች ፡
ለኢትዮጵያ ፡ ጀግኖች ፡ ለጦር ፡ ሠራዊቶች ፡

የእኛ ፡ ጦር ፡ ሠራዊት ፡ ባለቁምጣ ፡ ሱሪ ፡
ጠላትን ፡ ድል ፡ አድራጊ፡ምቀኛ ፡ አሳፋሪ ፡
ወገኑን ፡ አስመስጋኝ ፡ አገር ፡ አስከባሪ ፡
የምቀኛን ፡ መንፈስ ፡ በጸሎት ፡ ሰባሪ ።
እንኳን ፡ በምድርና ፡ በሰማይ ፡ ቢመጡ ፡
ይመልሱዋቸዋል ፡ ተስፋ ፡ እያስቆረጡ ፡
እጅና ፡ እግራቸውን ፡ እየቆራረጡ ፡
በዲሞትፈር ፡ ጥይት ፡ እየለመጠጡ ፡
እንዳይመለሱ ፡ ዳግመኛ ፡ እንዳይመጡ ።
ማመስገን ፡ ይገባል ፡ በውነት ፡ እነሱን ፡
መከታችን ፡ ናቸው ፡ ዙሪያ ፡ ጠረፉን ፡
እንዲህ ፡ መኖራችን ፡ በነፃ ፡ ኩርተን ፡
እግዜር ፡ ቢሰጠን ፡ ነው፡በውነት ፡ እነሱን ፡
በጣም ፡ ያርዝምልን ፡ ሕይወታቸውን ።
አደራህ ፡ ጌታችን ፡ በጣም ፡ ጠብቃቸው ፡
ዘላለም ፡ መኩሪያችን፡ መመኪያችን፡ናቸው ።
ተምሮ ፡ ሲያስተምር ፡ ሲያካፍል ፡ ዕውቀት ፡
በጣም ፡ ያስደስታል ፡ ያገሬ ፡ ወጣት ፡
ተማሪው ፡ ሲቀበል ፡ ሲበላ ፡ እንደሸት ፡
ተመልካቹ ፡ ሁሉ ፡ ማታና ፡ ጠዋት ፡
ሲደሰት ፡ ይውላል ፡ ይኸን ፡ በማየት ፡
መጣጣር ፡ ዛሬ ፡ ነው ፡ በወጣትነት ፡
ካረጁማ ፡ ወዲያ ፡ ካወጡ ፡ ሽበት ፡
ሚስት ፡ ካገቡና ፡ ከያዙ ፡ ንብረት ፡
አይገኝም ፡ ጊዜ ፡ ተግቶ ፡ ለማጥናት ፡
በጊዜ ፡ አትተኛ ፡ ተነሥ ፡ በጠዋት ፡
ገስግስና ፡ ግባ ፡ ከተማሪ ፡ ቤት ፡
ቁጭ ፡ ብለህ ፡ አጥና ፡ መልካሙን ፡ትምህርት ፡

ጠጣው ፡ እንደ ፡ ወተት ፡ ብላው፡እንደሽት ።
አይዞህ ፡ ያገሬ ፡ ልጅ ፡ የኔ ፡ ወንድም ፡ በርታ ፡
አጥና ፡ ትምርትህን ፡ ጠዋትና ፡ ማታ ።
የሀገሬ ፡ ወጣት ፡ ስማኝ ፡ ልምከርህ ፡
በወጣትነትህ ፡ ሁሉን ፡ ተምረህ ፡
ልዩ ፡ ልዩ ፡ ጥበብ ፡ ሥራ ፡ ላገርህ ፡
ኩራ ፡ ደስ ፡ ይበልህ ፡ በነፃነትህ ፡
ዕድሜ ፡ ለተፈሪ ፡ ለደጉ ፡ ጌታህ ።

ኢትዮጵያ ፤ እናንተ ፡ ወጣቶች ፡ ሎንዶን ፡ ላይ ፡ ያላችሁ ፡
እንደ ፡ ትኩስ ፡ ወተት ፡ ዕውቀት፡የጠጣችሁ ፡
እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ከዚህ ፡ ከሄዳችሁ ፡
እጅጉን ፡ ብዙውን ፡ እንደምንድናችሁ ፡
አደራ ፡ ልጆቼ ፡ ስለ ፡ ትምህርታችሁ ፡
በርቱ ፡ በጣም ፡ ትጉ ፡ ለራስ ፡ ለራሳችሁ ፡
እንድትመጡልኝ ፡ ጥበብን ፡ ለብሳችሁ ።

ወጣቶች ፤ ኢትዮጵያ ፡ እናታችን ፡ ዓለሚቱ ፡ ሆይ ፡
ከጠቅል ፡ ጋራ ፡ አለሽልን ፡ ወይ ።
የእኛ ፡ እመቤታችን ፡ ውዲቱ ፡ ደጊቱ ፡
የማትጠገቢው ፡ ዘላለም ፡ ወርቂቱ ፡
ለሕዝብሽ ፡ አሣቢ ፡ አጥብቀሽ ፡ በብርቱ ፡
ላንቺ ፡ እንዲሆንልን ፡ ሙሉ ፡ ጤንነቱ ፡
እንለምናለን ፡ አምላክን ፡ በብርቱ ።

ደራሲ ፤ የሀገሬ ፡ ጀግና ፡ ስማኝ ፡ ልምከርህ ፡
በሙሉ ፡ ልቦናህ ፡ ሥራ ፡ ላገርህ ፡
ጠንክር ፡ በጀግንነት ፡ እንደ ፡ ፊተኛህ ፡
ብትሞትም ፡ አይቆጭህ ፡ ለነፃነትህ ፡
ዋጋህን ፡ አታጣም ፡ ከደጉ ፡ ጌታህ ፡
በወርቃዊ ፡ ቀለም ፡ ተጽፎ ፡ ስምህ ፡

ታትሞ ፡ ይገኛል ፡ ከነታሪክህ ።
ያገሬ ፡ ወጣቶች ፡ እናንት ፡ ጀግኖቹ ፡
ጠንክራችሁ ፡ ሥሩ ፡ እንደፊተኞቹ ።
ጠንክራችሁ ፡ ሥሩ ፡ ብዬ ፡ ስላችሁ ፡
እናንተን ፡ ማዘዜ ፡ እንዳይመስላችሁ ።
ጠንክረን ፡ እንሥራ ፡ እኛ ፡ ሁላችን ፡
በፍቅር ፡ ተባብረን ፡ ለሀገራችን ፡
ዕድሜ ፡ ለተፈሪ ፡ ለንጉሣችን ፡
እንጻፍ ፡ ምስጋና ፡ እያንዳንዳችን ፡
ለዚች ፡ ለላምለሚ ፡ ለባንዲራችን ።
ለሀገሬ ፡ ጀግኖች ፡ ሰላምታ ፡ አቀርባለሁ ፡
ለሞቱት ፡ አርበኞች ፡ በጣም ፡ አዝኜአለሁ ።
እናንት ፡ ብትሞቱ ፡ አልሞተም ፡ ስማችሁ ፡
ታንጾ ፡ ተቀምጦአል ፡ ከነታሪካችሁ ።
ከመካከላችሁ ፡ አንዱ ፡ ደልጋ ፡ አንበሳ ፡
የራስ ፡ ደስታ ፡ ሰው ፡ ፊታውራሪ ፡ ካሣ ።
ገና ፡ ትንሽ ፡ ሆኖ ፡ በወጣትነቱ ፡
ይወራረድ ፡ ነበር ፡ ተኩሶ ፡ ላይስት ።
አይመታም ፡ ነበረ ፡ ደግሞ ፡ እሌላ ፡ ላይ ፡
ወይ ፡ ከጉልበት፡በታች ፡ ወይ ፡ ካንገት፡በላይ ፡
እያደራረበ ፡ አንዱን ፡ ባንዱ ፡ ላ ፡ ።
በሀገራችን ፡ ላይ ፡ ሲገባ ፡ ጠላት ፡
ጦር ፡ አበጋዝ ፡ ሆኖ ፡ ቀድሞ ፡ እፊት፡እፊት ፡
ሲዋጋ ፡ ሰንብቶ ፡ በቈራጥነት ፡
ሲቆላው ፡ ሲጠብሰው ፡ በመውዜር ፡ ጥይት ፡
እንደዚህ ፡ ሲዋጋ ፡ በወጣትነት ፡
ሀገሩን ፡ ሲረዳ ፡ በቈራጥነት ፡
ያሳዝን ፡ ነበረ ፡ ለመላው ፡ ፍጥረት ፡

ውሀ ፡ ጠማኝ ፡ ሲለው ፡ ያገሩ ፡ ጠላት ፡
ሲያጠጣው ፡ ዋለና ፡ የመውዜር ፡ ጥይት ፡
ጠላትም ፡ ሊሸነፍ ፡ ሲቀረው ፡ ጥቂት ፡
በድንገት ፡ ተመታ ፡ እጁን ፡ በጥይት ።
ቆስሎ ፡ በጠላት ፡ እጅ ፡ መማረክን ፡ ጠልቶ
በገዛ ፡ እጁ ፡ ዐረፈ ፡ ሽጉጡን ፡ ጠጥቶ ።
ገና ፡ ወጣት ፡ ነበር ፡ ለጋ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡
ሞተ ፡ ካሣ ፡ አግለው ፡ አገሩን ፡ ሲረዳ ።
ጀግና ፡ የጀግና ፡ ልጅ ፡ መዋጋት ፡ እንዲህ ፡ ነው ፡
ብትሞት ፡ ለባንዲራህ ፡ ለነፃነትህ ፡ ነው ።
ወንድምህ ፡ ደምሴ ፡ አዝኖ ፡ ላንተ ፡ ብዙ ፡
ቀይ ፡ የነበረው ፡ ሰው ፡ ጥቁር ፡ ሆኗል ፡ ወዙ ።
አትነሣም ፡ እንጂ ፡ ብታየው ፡ መጥተህ ፡
አታውቀውም ፡ ነበር ፡ ወንድሜ ፡ ብለህ ።
ሐዘንም ፡ አታብዛ ፡ እያደርክ ፡ እርሳው ፡
አምላክ ፡ መጥኔ ፡ ይስጥህ ፡ ደምሴ ፡ አግለው ።
እንዲህ ፡ ያለ ፡ ጀግና ፡ ቀረ ፡ በወጣትነቱ ፡
ምስጋናው ፡ ታሪኩ ፡ አያልቅም ፡ በጥቂቱ ።
እጽፍለት ፡ ነበር ፡ ታሪኩን ፡ በዝርዝር ፡
ጊዜ ፡ ስላጠረኝ ፡ ትቼዋለሁ ፡ ይቅር ።
ቢሞት ፡ በጀግንነት ፡ አፈር ፡ ቢጫነው ፡
ዘለዓለም ፡ አይሞትም ፡ ታሪክ ፡ ያለው ፡ ሰው ።
ይማራቸው ፡ እንጂ ፡ በሰማይ ፡ እግዜር ፡
ከሱ ፡ ጋር ፡ የሞቱት ፡ የሆኑት ፡ አፈር ፡
እጽፋቸው ፡ ነበር ፡ ሁሉን ፡ በዝርዝር ፡
ጊዜ ፡ ስለሚፈጅ ፡ ይሁን ፡ በድምር ።
ከጅብ ፡ አፍ ፡ አውጥቶኝ ፡ ለዚህ ፡ ካበቃኝ ፡
ሀገሬን ፡ ላመስግን ፡ እንደሚቻለኝ ፡

እኔን ፡ ደስ ፡ ብሎኛል ፡ ተነሣሽ ፡ ቢሉኝ ፡
ያገሬ ፡ ባንዲራ ፡ ለዘለዓለም ፡ ጽኝ ።
ትጣፍጭኛለሽ ፡ ከማር ፡ ከወተት ፡
አገሬ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ሁኝ ፡ መሠረት ፡
እንደ ፡ እናት ፡ እንጐቻ ፡ እንደ ፡ ልጅነት ፡
ቅር ፡ ቅር ፡ የምትል ፡ ኢትዮጵያ ፡ ናት ።
ለእግዚአብሔር ፡ ምስጋና ፡ እናቀርባለን ፡
ከዚያ ፡ ጭንቅ ፡ አውጥቶ ፡ ይህን ፡ ለሰጠን ።
በዚያ ፡ በአምስት ፡ ዓመት ፡ ሲገዛን ፡ ፋሽስት ፡
ጨልሞብን ፡ ነበር ፡ ቀኑ ፡ እንደ ፡ ሌሊት ።
ተመስገን ፡ ጌታችን ፡ ከጭንቅ ፡ ያወጣኸን ፡
ያን ፡ መከራ ፡ ወስደህ ፡ ይህን ፡ የሰጠኸን ፡
ጌታችን ፡ አደራህ ፡ ልዑል ፡ አምላካችን ፡
ይንገሥ ፡ ለዘለዓለም ፡ ጠቅል ፡ አንበሳችን ፡
ተፈሪ ፡ ነውና ፡ ለእኛ ፡ ቀኝ ፡ እጃችን ፡
አረንጓዴ ፡ ብጫ ፡ ቀይ ፡ ሐር ፡ ባንዲራችን ፡
የጀግኖች ፡ ተስፋ ፡ ናት ፡ የወጣቶቻችን ፡
እሷን ፡ ያኑርልን ፡ ዘለዓለም ፡ ጌታችን ፡
እናቅርብ ፡ ምስጋና ፡ ለቸሩ ፡ አምላካችን ።
የሰው ፡ አገር ፡ አትክልት ፡ ደርቆ ፡ እንደገለባ ፡
በኢትዮጵያ ፡ መሬት ፡ አለ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡
ያውም ፡ የደመቀ ፡ ካበባም ፡ አበባ ።
የጠገበ ፡ ፈረስ ፡ ገብቶ ፡ ሀገራችን ፡
በእግሩ ፡ እየረገጠን ፡ ከወደ ፡ ኋላችን ፡
ተፈሪ ፡ አባ ፡ ጠቅል ፡ ደጉ ፡ ንጉሣችን ፡
ከሎንዶን ፡ ገሥግሦ ፡ ደርሶ ፡ በነፍሳችን ፡
ጋማውን ፡ መልምሎ ፡ እዚህ ፡ እፊታችን ፡
ባውራሪስ ፡ ሲገርፈው ፡ አየነው ፡ ባይናችን ፡

በኢትዮጵያ ፡ መሬት ፡ መች ፡በደህናው፡ገባ ፡
አምላክ ፡ ፈርዶበት ፡ ነው ፡ እጕድጓድ፡ሊገባ።
እግዚአብሔር ፡ ሲቆጣው ፡ ከሀገሩ ፡ ወጥቶ ፡
አፈር ፡ ሆኖ ፡ ቀረ ፡ በሰው ፡ አገር ፡ ገብቶ ።
ቢቀር ፡ ይሻል ፡ ነበር ፡ እንደኔ ፡ ቢሆን ።
በሰው ፡ አገር ፡ ገብቶ ፡ አፈር ፡ ከመሆን ።
በደህናህ ፡ አይደለም ፡ ያቅነዘነዘህ ፡
ተሮማ ፡ ተነስተህ ፡ እዚህ ፡ መምጣትህ ።
ደምህ ፡ ሊፈስ ፡ ነው ፡ ሊረግፍ ፡ አጥንትህ ።
ደግሞ ፡ ሕዝባችንን ፡ ባሰት ፡ ሲያታልለው
አንዱን፡ሳርጃ፡ማጆር፡አንዱን፡ሹምባሽ፡አለው
የማይሆንላትን ፡ ይች ፡ የሮማ ፡ አሞራ ፡
ደግሞ ፡ ጠብ ፡ ማብቀሏ ፡ ካንበሳችን ፡ ጋራ ።
የሚካኤል ፡ ለታ ፡ በየካቲት ፡ ወር ፡
ቦንብ ፡ ተተኩሶ ፡ ሆኖብን ፡ ሽብር ፡
በጣም ፡ በዝቶ ፡ ነበር ፡ ሆኖ ፡ ግርግር ፡
የዚያ ፡ ለት ፡ የሞተው ፡ ያለቀው ፡ ፍጡር ፡
ይኸ ፡ ነው ፡ ተብሎ ፡ የለውም ፡ ድምር ፡
ሊገመት ፡ አይችልም ፡ እንኳን ፡ በዝርዝር ፡
ይቅር ፡ አይወራ ፡ የያኔው ፡ ታምር ።
እንደዚሁ ፡ ደግሞ ፡ ብዙውን ፡ ፍጥረት ፡
በሳት ፡ ሲያቃጥሉት ፡ እየዘጉ ፡ ቤት ፡
የተረፈውንም ፡ ከዚያ ፡ ከጭንቀት ፡
ወደ ፡ ደናኔ ፡ አገር ፡ ሄዱ ፡ ይዘውት ፡
እርጉዝ ፡ ስታቃስት ፡ ሲጮህ ፡ ሕፃናት ፡
ሽማግሌ ፡ አሮጊት ፡ ሲሉ ፡ አቤት ፡ አቤት ።
ሃምሳ ፡ ሃምሳውን ፡ ሰው ፡ አብረው ፡አፍገው፡
እንዲሁም ፡ የሞተው ፡ ብዙ ፡ ሕፃን ፡ ነው ።

## አበባዬ ፡ ፍቅሬ ።

እንድ ፡ ንጉሥ ፡ ወልዶ ፡ ሁለት ፡ ልጆች ፡
አንድ ፡ ወንድ ፡ አንድ፡ሴት፡ቆንጆ፡ቆንጆዎች ፡
እንዲሁም ፡ ሴቷ ፡ ልጅ ፡ በጣም ፡ ቀይ ፡ ነች ፡
እንደ ፡ አልማዝ ፡ እንደ፡ወርቅ፡ያብረቀረቀች ፡
ፍጥረት ፡ የቀናባት ፡ ውብት ፡ የሆነች ፡
እንደ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ የለሰለሰች ።
እጅግ ፡ ያለመጠን ፡ አባቷ ፡ ወዷት ፡
ከፍተኛ ፡ ፎቅ ፡ ቤት ፡ አሠርቶላት ፡
የቄስ ፡ አስተማሪ ፡ ቀጥሮ ፡ አምጥቶላት ፡
እንድትማርለት ፡ መልካሙን ፡ ትምህርት ፡
እያበረታታ ፡ ማታና ፡ ጠዋት ፡
አይዞሽ ፡ በርቺ ፡ ልጄ ፡ ጠንክሪ ፡ እያላት ፡
ወደ ፡ መንገድ ፡ ሲሄድ ፡ ተነሥቶ ፡ ድንገት ፡
እስከመጣ ፡ ድረስ ፡ ከምሄድበት ፡
እንዳትበዝኚ ፡ ለያዝሽው ፡ ትምህርት ፡
እመጣለሁና ፡ ቶሎ ፡ በፍጥነት ።
አይዞሽ ፡ የኔ ፡ አበባ ፡ ቅርም ፡ አይበልሽ ፡
ፈጥነን ፡ እንመጣለን ፡ እኔና ፡ እናትሽ ፡
ቄሱም ፡ ደህና ፡ ሰው፡ነው፡ያንቺ፡አስተማሪሽ ፡
እነግርልሻለሁ ፡ እንዲያስተምርሽ ፡
በጣም ፡ እንዲያስጠናሽ ፡ እንዲገልጽልሽ ፡
ደጃዝማችም ፡ አለ ፡ ቅርም ፡ አይበልሽ ፡
ጭራሽ ፡ አታስቢ ፡ አይፍራ ፡ ሆድሽ ፡
እንዳትባልጊ ፡ ሰው ፡ እንዳይሰድብሽ ፡
በጣም ፡ አጥብቄ ፡ ነው ፡ አደራ ፡ ስልሽ ።
ቄሱንም ፡ ሄደና ፡ የልጄን ፡ ነገር ፡

አደራ ፡ በሰማይ ፡ አደራ ፡ በምድር ፡
እንድትማር ፡ ይሁን ፡ እንድትጠነክር ።
ደጃዝንማቹ ፡ ደግሞ ፡ እንግዲህ ፡ አደራ ፡
ልጇን ፡ ጠብቅልኝ ፡ ከመምሕሩ ፡ ጋራ ።
ባንተ ፡ ላይ ፡ ጥያለሁ ፡ አደራ ፡ የቤቴን ፡
የትዳሬን ፡ ነገር ፡ የመላ ፡ ንብረቴን ።
እኔ ፡ መሄዴ ፡ ነው ፡ ለብርቱ ፡ ነገር ፡
ድንገት ፡ ተነስቼ ፡ ወደውጪ ፡ አገር ፡
አደራ ፡ ጥያለሁ ፡ በሰማይ ፡ በምድር ፡
እንዳልሰማ ፡ ክፉ ፡ የልጇን ፡ ነገር ።
ብሎ ፡ ወዲያውኑ ፡ ጉዞውን ፡ ቀጠለ ፡
ቄሱም ፡ ያለመጠን ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ ዋለ ፡
ወዲያውም ፡ ጠየቃት ፡ እንደዚህ ፡ እያለ ።
አብረን ፡ እንተኛ ፡ ቆንጆት ፡ እባክሽ ፡
ሁሉን ፡ በያይነቱ ፡ እንዳስተምርሽ ፡
ለሰውም ፡ አልነግር ፡ በፍጹም ፡ ጭራሽ ፡
አይዞሽ ፡ ግድ ፡ የለሽም ፡ አይፍራ ፡ ሆድሽ ፡
እንዲህ ፡ ስለምንሽ ፡ እኔን ፡ ታሳፈርሽ ፡
እንኳን ፡ ላስተምርሽ ፡ ዞሬም ፡ አላይሽ ።
ብሎ ፡ ቢጠይቃት ፡ ልጅቱ ፡ ደንግጣ ፡
ታለቅስ ፡ ጀመረች ፡ በመስኮት ፡ ተቀምጣ ።
ደግሞ ፡ ደጃዝማቹ ፡ መጣና ፡ ከቤት ፡
ይለምናት ፡ ጀመር ፡ እንዲህ ፡ በማለት ፡
ብቅ ፡ ብለሽ ፡ ሳይሽ ፡ እኔ ፡ በመስኮት ፡
እደነግጣለሁ ፡ እህቴ ፡ በውነት ፡
አጥብቄ ፡ እመኛለሁ ፡ ማታና ፡ ጠዋት ፡
አንድ ፡ ቀን ፡ ካንቺ ፡ ጋር ፡ ለመገናኘት ፡
እንዳታሳፍሪኝ ፡ ፍቅሬ ፡ የኔ ፡ እኅት ።

ይኸንን ፡ ስትሰማ ፡ አካላቷ ፡ አለቀ ፡
ያስለቅሳት ፡ ጀመር ፡ እያንሰቀሰቀ ።
ቂሱም ፡ ደጃዝማቹም ፡ ደፍረው ፡ ቢናገሯት ፡
ሕይወቷ ፡ ያለፈ ፡ የሞተች ፡ መሰላት ።
ትናደድ ፡ ጀመረ ፡ እነሱን ፡ ስታይ ፡
በፍጹም ፡ መሰሏት ፡ ያባቷ ፡ ገዳይ ።
ወዲያውም ፡ ልጅቷ ፡ መለሰችለት ፡
እያስተዛዘነች ፡ እንዲህ ፡ በማለት ፡
እኔ ፡ ያንተ ፡ ልጅ ፡ ነኝ ፡ አንተ ፡ የኔ ፡ አባት ፡
ፍጹም ፡ አንተና ፡ እኔ ፡ ለመገናኘት ፡
ኰነኔ ፡ ያመጣል ፡ በላይኛው ፡ ቤት ።
አዝናለሁ ፡ በብዙ ፡ ባንተ ፡ በራስህ ፡
እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ በመናገርህ ።
ትልቅ ፡ ሰው ፡ መስለኸኝ ፡ አከብርህ ፡ ነበር ፡
ለካስ ፡ ትንሽ ፡ ልጅ ፡ ነህ ፡ ገና ፡ እምር ፡ ታህል ።
ጥንት ፡ ትልቅ ፡ ነበር ፡ በጣም ፡ እራስህ ፡
እያነሰ ፡ ሄደ ፡ እየቀለለህ ፡
ለአንተ ፡ በይታይህ ፡ ባይታወቅህ ፡
በግልጽ ፡ ይታየኛል ፡ እኔ ፡ ልንገርህ ።
ይኸንን ፡ ሲሰማ ፡ እየተናደደ ፡
ምንም ፡ ሳይናገር ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ፡
ጨሶ ፡ ተቃጠለ ፡ አንጀቱ ፡ ነደደ ፡
እንደሰከረ ፡ ሰው ፡ ጭራሽ ፡ እንዳበደ ፡
ያስኬደው ፡ ጀመረ ፡ እያንገደገደ ።
እንዲሁም ፡ አባቷ ፡ ሆነው ፡ ካሉበት ፡
አልችልህ ፡ ብለውት ፡ የእሷን ፡ ናፍቆት ፡
ልጃቸውን ፡ አሉት ፡ ሄደህ ፡ ጠይቃት ።
ልጁም ፡ እሺ ፡ ብሎ ፡ እየገሠገሠ ፡

ከዚያው ፡ ካለችበት ፡ በፍጥነት ፡ ደረሰ ።
ወዲያው ፡ ተገናኝተው ፡ ከደጃዝማች ፡ ጋራ ፡
ይጠይቀው ፡ ጀመር ፡ ያባቱን ፡ አደራ ።
ደጃዝማችም ፡ አለው ፡ ቤቱ ፡ ደህና ፡ ነው ፡
ልጅቷ ፡ ብቻ ፡ ናት ፡ የባለገችው ፡
በጭራሽ ፡ ግቢውን ፡ ያበላሸችው ፡
ሥራዋ ፡ በሙሉ ፡ የሚያሳዝን ፡ ነው ።
መኳንንቱን ፡ ሁሉ ፡ እየሰደበች ፡
ትልልቁን ፡ ሰዎች ፡ እያዋረደች ፡
ለግድያ ፡ ደርሰው ፡ ብዙ ፡ ጐረምሶች ፡
በጭራሽ ፡ ሸርሙጣ ፡ እብድ ፡ ሆናለች ።
ልጁም ፡ ደነገጠ ፡ ይህን ፡ በመስማት ፡
በውነት ፡ ያደረገች ፡ የሠራች ፡ መስሎት ፡
ተመልሶ ፡ ሄደ ፡ ወደ ፡ መጣበት ።
ላባቱ ፡ ነገረው ፡ ዘርዝሮ ፡ ሁሉን ፡
ወዲያውም ፡ ሲሰማ ፡ አባቷ ፡ ይኸን ።
ልጅየውን ፡ አለው ፡ በቶሎ ፡ ሄደህ ፡
እሷን ፡ እረድና ፡ ሥጋዋን ፡ ቀብረህ ፡
አምጣልኝ ፡ ከደሟ ፡ በጠርሙስ ፡ ቀድተህ ።
ልጁም ፡ እሺ ፡ ብሎ ፡ እንደታዘዘው ፡
ትእዛዙን ፡ ሊፈጽም ፡ አባቱ ፡ እንዳለው ፡
ሲገሰግስ ፡ ሄደ ፡ ደረሰ ፡ ወዲያው ።
ድንገት ፡ ደረሰና ፡ ካለችበት ፡ ቤት ፡
ወዲያው ፡ ተነሽ ፡ ብሎ ፡ ሄደና ፡ ይዟት ፡
እዚያው ፡ አጠገቡ ፡ ቁጭ ፡ በይ ፡ ብሏት ፡
ጉድጓዱን ፡ ሲቆፍር ፡ አርዶ ፡ ሊቀብራት ፡
ስለ ፡ ደከመና ፡ ስለ ፡ አሳዘናት ፡
ትጠይቀው ፡ ጀመር ፡ እንዲህ ፡ በማለት ።
ምነው ፡ የእናቴ ፡ ልጅ ፡ ፍቅሬ ፡ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡

እናትና ፡ አባቴ ፡ ደህናም ፡ አይደሉ ፡ ወይ ።
ወይ ፡ አባቴ ፡ ሞተ ፡ ወይንስ ፡ እናቴ ፡
እባክህ ፡ ንገረኝ ፡ ወንድሜ ፡ በሞቴ ።
ብላ ፡ በማሳዘን ፡ ጋሽዬ ፡ እያለች ፡
ቃሏን ፡ በማለስለስ ፡ እያለቀሰች ፡
ላቡን ፡ በመሐረብ ፡ እየጠረገች ።
መልሳ ፡ ቀልሳ ፡ ስለጠየቀችው ፡
በጣም ፡ ያለመጠን ፡ ስለ ፡ አሳዘነችው ።
እንግዲህ ፡ እህቴ ፡ ልንገርሽ ፡ አላት ፡
የሠራሽው ፡ ሥራ ፡ ባባታችን ፡ ቤት ፡
እየተሳደብሽ ፡ ብዙ ፡ መኳንንት ፡
ሽርሙጥነት ፡ ይዞሽ ፡ ትተሽ ፡ ትምህርት ፡
ይኸን ፡ ነገር ፡ ሰምቶ ፡ ደግሞ ፡ የእኛ ፡ አባት ፡
ተናዶ ፡ ተቃጥሎ ፡ ደርሶ ፡ ለመሞት ፡
እኔንም ፡ አዘዘኝ ፡ እንዲህ ፡ በማለት ።
እሷን ፡ እረድና ፡ ሥጋዋን ፡ ቀብረህ ፡
አምጣልኝ ፡ ከደሟ ፡ በጠርሙስ ፡ ቀድተህ ።
እኔም ፡ ተቆጥቼ ፡ በጣም ፡ ተናድጄ ፡
አባቴ ፡ እንዳዘዘኝ ፡ ልቀብርሽ ፡ አርጄ ፡
ነበር ፡ የመጣሁት ፡ መሞትሽን ፡ ፈቅጄ ።
አሁን ፡ ግን ፡ በለቅሶሽ ፡ ባጠያየቅሽ ፡
እንባሽ ፡ አሳዘነኝ ፡ እንኳንስ ፡ ደምሽ ፡
ብትሞችም ፡ በመንገድ ፡ ጅብም ፡ ቢበላሽ ፡
ቸሩ ፡ መድኃኔ ፡ ዓለም ፡ ባወጣ ፡ ያውጣሽ ፡
ጥፊ ፡ ካጠገቤ ፡ ዓይኔም ፡ አይይሽ ።
ብሎ ፡ እያለቀሰ ፡ ሆዱን ፡ አጥናናና ፡
አንዲት ፡ የበግ ፡ ግልገል ፡ ከቤት ፡ አወጣና ፡
በሰላ ፡ ቢላዎ ፡ እሷን ፡ አረደና ፡

ሬሳውን ፡ ቀብሮ ፡ ከደሟ ፡ ቀዳና ፡
ሰጠው ፡ ለአባትየው ፡ አረድኳት ፡ አለና ።
አባቷም ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ ደሟን ፡ በማየቱ
ወዲያውም ፡ ጠጣና ፡ ነገራት ፡ ለሚስቱ ።
እኔና ፡ አንች ፡ ድንገት ፡ ወደዚህ ፡ ብንመጣ
በጣም ፡ ተበላሽታ ፡ ልጃችን ፡ ሸርሙጣ ።
መኳንንቱን ፡ ሁሉ ፡ እየሰደበች ፡
የቤት ፡ አሽከሮቹን ፡ እያዋረደች ፡
ትምህርቷንም ፡ ትታ ፡ ስለባለገች ፡
ደሟንም ፡ ጠጣሁት ፡ እሷም ፡ ታረደች ።
እናቷም ፡ መለሰች ፡ እንዲህ ፡ እያለች ፡
እንዲህ ፡ ያለ ፡ በደል ፡ በእውነት ፡ ከሠራች
ሙሉ ፡ ፈቃዴ ፡ ነው ፡ እንኳን ፡ ታረደች ፡
ጭራሽ ፡ ክጃታለሁ ፡ ልጄም ፡ አይደለች ።
ብላ ፡ ተናገረች ፡ እናቷ ፡ ተናዳ ፡
ባንድ ፡ በኩል ፡ ደግሞ ፡ አልችል ፡ ብሷት ፡ ሆዷ
ቃለቅስ ፡ ነበረ ፡ ገብታ ፡ ወደ ፡ ጓዳ ።
እናትና ፡ አባቷ ፡ ተነሥተው ፡ ወዲያው ፡
ግስጋሴ ፡ ያዙ ፡ ወደቤታቸው ፡
ወዲያው ፡ ከመንገዱ ፡ በደህና ፡ ደርሰው ፡
ከደጃዝማቻቸው ፡ ጋር ፡ ተገናኝተው ፡
ይጠይቁት ፡ ጀመር ፡ ስለአደራቸው ።
ደጃዝማቹም ፡ ደግሞ ፡ እንደለመደ ፡
ይዋሽ ፡ ነበረ ፡ እየጎማመደ ።
የርስዎ ፡ ልጅማ ፡ የሠራችው ፡ ሥራ ፡
ብተወው ፡ ይሻላል ፡ ጭራሽ ፡ ባይወራ ፡
አዳርዋ ፡ ውሎዋ ፡ ከጐረምሶች ፡ ጋራ ።
ሸርሙጥነት ፡ ይዛ ፡ ቀረና ፡ መማርዋ ፡

ትልቅ ፡ ሰው ፡ ስትሰድብ ፡ ደግሞ ፡ አለማፈርዋ ።
እኔ ፡ አንኳ ፡ እራሴ ፡ ቀ፫፪ቤአት ፡ ስታ፱ ፡
ትሰድበኝ ፡ ነበረ ፡ እንደ ፡ አንድ ፡ አገልጋይ ።
አለና ፡ ቢነግረው ፡ ላባቷ ፡ በውሸት ፡
ጭራሹን ፡ ሆነበት ፡ በንዴት ፡ ላይ ፡ ንዴት ።
ወዲያውም ፡ ሲጐበኙ ፡ ግቢዎችን ፡ ሁሉ ፡
ያስቀሰችበት ፡ ያች ፡ ልጅ ፡ በሙሉ ፡
በጣም ፡ የሚያስደንቅ ፡ ስለ ፡ አበቃቀሉ ።
በመኖሪያ ፡ ቤትዋ ፡ ከግድግዳው ፡ ስር ፡
በብዙ ፡ ቀጤማ ፡ አብቅሎ ፡ ነበር ።
እናትና ፡ አባቷ ፡ ወዲያው ፡ እሱን ፡ አይተው ፡
እየተገረሙ ፡ በጣም ፡ ተመልክተው ፡
ደጃዝማቻቸውን ፡ ወዲያው ፡ አስጠርተው ፡
ይጠይቁት ፡ ጀመር ፡ በብርቱ ፡ አጥርተው ፡
ደጃዝማቹም ፡ ደግሞ ፡ እንደዚህ ፡ አላቸው ።
ልጅቷ ፡ ዘወትር ፡ ማታና ፡ ጠዋት ፡
አረቄና ፡ ጠጁን ፡ ስታፈስበት ፡
ቀጤማ ፡ አበቀለ ፡ ይኸውም ፡ መሬት ።
እናትና ፡ አባቷም ፡ እየተናደዱ ፡
ብለው ፡ አዘዙና ፡ በሉ ፡ አሁን ፡ እጩዱ ፡
እሱን ፡ አለፉና ፡ ወደሌላ ፡ ሄዱ ፡
ደግሞ ፡ እንደ ፡ ታዘዙ ፡ አሽከሮቹ ፡ ሲያጭዱ ፡
መልሶ ፡ በቀለ ፡ ከስሩ ፡ ሳይሄዱ ፡
እናትና ፡ አባቷም ፡ ምን ፡ ይባላል ፡ ጉዱ ፡
በሉ ፡ ድገሙና ፡ አሁንም ፡ እጨዱ ፡
ብለው ፡ አዘዙና ፡ ወዴትም ፡ ሳይሄዱ ፡
እዚያው ፡ አጠገቡ ፡ ቆመው ፡ አሳጨዱ ፡
አሁንም ፡ መልሶ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ልማዱ ፡
በቀለ ፡ ቀጤማው ፡ አላለቀም ፡ ጉዱ ።

እናትና ፡ አባቷም ፡ ገርሟቸው ፡ ነገሩ ፡
ንቀሉልን ፡ አሉ ፡ በጭራሽ ፡ ከሥሩ ።
ወዲያው ፡ አሽከሮቹ ፡ እንደታዘዙት ፡
ቆፍረው ፡ ከሥሩ ፡ ነቃቅለው ፡ ጣሉት ።
ይህችም ፡ ቆንጆ ፡ ልጅ ፡ የተበደለች ፡
በበረሃ ፡ ስትሄድ ፡ እያለቀሰች ።
ጠፍታ ፡ ስትኰበልል ፡ በቆራጥነት ፡
አንዲት ፡ ልጅ ፡ አገረድ ፡ አግኝታ ፡ ድንገት ።
እባክሽ ፡ አንች ፡ ልጅ ፡ የምለምንሽን
አውልቂና ፡ ስጭኝ ፡ የውስጥ ፡ ልብስሽን ።
ልጅቷም ፡ ሰጠቻት ፡ ቀሚሷን ፡ አውልቃ ፡
በድንገት ፡ መጥፋቷን ፡ መኰብለሏን ፡ ዐውቃ
ወዲያውም ፡ ሸኘቻት ፡ መንገድ ፡ አሳይታ ።
እሷም ፡ ደስ ፡ ብሏት ፡ ቀሚስ ፡ በማግኘቷ
የለበሰችውን ፡ ስትወጣ ፡ ከቤቷ ፡
ሐር ፡ ስለነበር ፡ ያሰፋው ፡ አባቷ ።
ያንን ፡ ሐር ፡ ቀሚስ ፡ አውልቃ ፡ ጠቅልላ ፡
ጉዞዋን ፡ ቀጠለች ፡ በትከሻዋ ፡ አዝላ ።
ስትሄድ ፡ ቆይታ ፡ ችጋር ፡ ቢይዛት ፡
ምንተ ፡ ማርያም ፡ ብላ ፡ ገባች ፡ ከንጉሥ ፡ ቤት ።
ንጉሡም ፡ አዩና ፡ ቆማ ፡ ስትለምን ፡
ቶሎ ፡ ስጡአት ፡ አሉ ፡ መብል ፡ ምናምን ።
ወዲያውም ፡ አንዲቷ ፡ የንጉሡ ፡ ገረድ ፡
እንጀራ ፡ ልትሰጣት ፡ ይዛ ፡ ስትሄድ ።
አንችስ ፡ መላክ ፡ እንጂ ፡ ሰውስ ፡ አይደለሽም
እንደለማኝ ፡ ምግብ ፡ ፍጹም ፡ አልሰጥሽም
ብላ ፡ ተመለሰች ፡ እህሉንም ፡ መልሳ ፡
ለንጉሡ ፡ ነገረች ፡ ቃልዋን ፡ አለስልሣ ።

ያች ፡ የቆመች ፡ ልጅ ፡ ከዚህ ፡ ከኛ ፡ ደጅ ፡
ሰው፡ አትመስለኝም ፡ መልአክ ፡ ነች ፡ እንጅ ።
ንጉሡም ፡ መለሱ ፡ ነይ ፡ ግቢ ፡ በያት ፡
ምን ፡ ሰው ፡ እንደሆነች ፡ አጥብቄ ፡ ልያት ።
ገረዷም ፡ አለቻት ፡ ንጉሦ ፡ ይጠሩሻል ፡
በተቻለ ፡ ፍጥነት ፡ ነይ ፡ ግቢ ፡ ይሉሻል ።
እሷም ፡ ሄደችና ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ፊት ፡
ይጠይቋት ፡ ጀመር ፡ እንዲህ ፡ በማለት ።
ያፈራ ፡ ብርቱካን ፡ ይመስላል ፡ ጉንጭሽ ፡
ደግሞም ፡ ሰውነትሽ ፡ ዓይንና ፡ ጥርስሽ ፡
የመልክሽ ፡ ቁንጅና ፡ ከነቅላትሽ ፡
የትስ ፡ ትሄጃለሽ ፡ ከየትስ ፡ መጣሽ ፡
እባክሽ ፡ ንገሪኝ ፡ እናት ፡ አባትሽ
በሕይወት ፡ እያሉ ፡ እንዴት ፡ ለቀቁሽ ።
ልጅቷም ፡ መለሰች ፡ ውሀ ፡ ጥም ፡ ይዞኛል ፡
ሰውነቴን ፡ ደግሞ ፡ ድካም ፡ ተሰምቶኛል ፡
እንደዚሁም ፡ እራብ ፡ በጣም ፡ በዝቶብኛል ፡
መናገር ፡ አልቻልኩም ፡ በጭራሽ ፡ ደክሞኛል ።
ንጉሡም ፡ አዘዙ ፡ እንጀራ ፡ ስጧት ፡
ትብላ ፡ ትጠጣና ፡ እንድትጫወት ፡
ሥራም ፡ አታሠሩዋት ፡ ትቀመጥ ፡ እቤት ፡
ጭራሽ ፡ አትዘዙዋት ፡ አትናገሩዋት ።
እንደዚሁም ፡ ደግሞ የሳቸውም ፡ ልጅ ፡
በሽተኛ ፡ ነበር ፡ አይወጣም ፡ እደጅ ።
ጤንነቱን ፡ አጥቶ ፡ ሆኖ ፡ ሕመምተኛ ፡
ሰባት ፡ ዓመቱ ፡ ነው ፡ ባልጋ ፡ ላይ ፡ ከተኛ ።
ይህም ፡ በሽተኛ ፡ እንጀራ ፡ ሲበላ ፡
አይውጥም ፡ ነበረ ፡ ካንድ ፡ ጉርሻ ፡ ሌላ ።

ደግሞ ፡ ይኽን ፡ ምግቡን ፡ የምትሠራለት ፡
ገረድ ፡ ነበረችው ፡ ልጅነት ፡ ያላት ።
ከዕለታት ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ድስት ፡ ስትሠራ ፡
ድስቱን ፡ እንደ ፡ ጣደች ፡ ገና ፡ ስታቁላላ ።
ሎጋው ፡ ሽበ ፡ እያለ ፡ ሠርገኛው ፡ ሲሄድ ፡
ልታዳምጥ ፡ ሄዳ ፡ ቆማ ፡ ከመንገድ ።
ወዲያውም ፡ ያች ፡ ልጅ ፡ ከቤት ፡ ተቀምጣ ፡
ሲቃጠል ፡ ብታየው ፡ አሮ ፡ እየተንጣጣ ።
ድስቱን ፡ ሠራችና ፡ እንደሚገባው ፡
አውጥታ ፡ አስቀመጠች ፡ እዚያው ፡ እበታው ፡
ሠርገኞቹም ፡ ሄደው ፡ ሲጨልም ፡ ጊዜው ፡
መጣች ፡ ገረዲቱ ፡ ድስቱን ፡ አስታውሳው ፡
ወጡንም ፡ ተሠርቶ ፡ ስላገኘችው ፡
ብላ ፡ ጠየቀቻት ፡ ማነው ፡ የሠራው ።
ልጅቱም ፡ መለሰች ፡ እኔ ፡ ነኝ ፡ እቴ ፡ ሆይ ፡
ይቅርታ ፡ አድርጊልኝ ፡ አጥፍቴ ፡ ይሆን ፡ ወይ ።
ገረዲም ፡ መለሰች ፡ እንኳን ፡ የሠራሽው ፡
በደንቡ ፡ ከሠራሽ ፡ በስሎ ፡ ካወጣሽው ።
ወዲያው ፡ ደረሰና ፡ የምግቡ ፡ ሰዓት ፡
ይኸ ፡ ሕመምተኛ ፡ ስጡኝ ፡ አለ ፡ እራት ።
እራቱም ፡ ቀረበ ፡ እንደተለመደው ፡
አንድ ፡ ጊዜ ፡ ጕርሶ ፡ ወጡንም ፡ ወደደው ።
አለና ፡ ጠየቀ ፡ ዛሬ ፡ ይህን ፡ ወጥ ፡
የሠራችልኝ ፡ ሴት ፡ የትኛዋ ፡ ናት ፡
ገረዲም ፡ መለሰች ፡ ያጠፋች ፡ መስሏት ፡
ይች ፡ ልጅ ፡ ነበረች ፡ እኔ ፡ ሳላያት ፡
እሱም ፡ ጥሪያት ፡ አለ ፡ ቶሎ ፡ በፍጥነት ፡
እሷም ፡ ትጠሪያለሽ ፡ ብላ ፡ ብትላት ፡

በጣም ፡ ደነገጠች ፡ ለቁጣ ፡ መስሎአት ፡
ልጁም ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ እሷን ፡ ጠየቃት፡
የሠራሽው ፡ ዛሬ ፡ አንቺ ፡ ነሽ ፡ ወይ ፡ ድስት ፡
እስዋም ፡ አዎን ፡ አለች ፡ ሆዷን ፡ ሲጨንቃት ፡
ሊቆጣኝ ፡ ነው ፡ ብላ ፡ ወድቃ ፡ በፍራት ።
እሱም ፡ በነገሩ ፡ እየተገረመ ፡
በልቶ ፡ የማያውቀውን ፡ ጭራሽ ፡ ከታመመ ።
አንድ ፡ እንጀራ ፡ በልቶ ፡ ያውም ፡ ሳይጠቅመው ፡
እናቱን ፡ ጠራና ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡
ይገርማል ፡ ይደንቃል ፡ የዛሬውስ ፡ ጉድ ፡ ነው ፡
አንድ ፡ እንጀራ ፡ በላሁ ፡ ምሕረትን ፡ ላገኝ ፡ ነው ።
ከዛሬም ፡ ጀምሮ ፡ የምበላውን ፡
የምታሰናዳ ፡ ይች ፡ ልጅ ፡ ትሁን ፡
እኔ ፡ አልፈልጋትም ፡ የፊተኛዋን ።
እናትና ፡ አባቱ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ አላቸው ፡
ምግቡን ፡ እንድትሠራ ፡ ሆነ ፡ ፈቃዳቸው ፡
እስዋም ፡ እየሠራች ፡ ስትመግበው ፡
ልክ ፡ በሳምንቱ ፡ ሆነ ፡ ደህና ፡ ሰው ።
በአሥራ ፡ አምስተኛው ፡ ቀን ፡ ሆኖ ፡ በፈረስ
ሄዶ ፡ ተመለሰ ፡ ብዙ ፡ አገር ፡ ድረስ ።
እንዲሁም ፡ ሲሆነው ፡ አንድ ፡ ወር ፡ ከሳምንት ፡
እምላክ ፡ ስለሰጠው ፡ ሙሉ ፡ ጤንነት ፡
አስበው ፡ አባቱ ፡ እንዲያገባ ፡ ሚስት ፡
አጥብቀው ፡ ጠየቁት ፡ እንዲይዝ ፡ ንብረት ።
እሱም ፡ ተናገረ ፡ ሚስት ፡ አግባ ፡ ካሉኝ ፡
ያችን ፡ ቀላቢዬን ፡ በሕግ ፡ ይዳሩኝ ፡
አለስዋ ፡ አላገባም ፡ እሞታለሁኝ ።
አባቱም ፡ መለሱ ፡ ጠይብ ፡ ትሁን ፡ ቡዳ ፡

የት ፣ ብሎ ፡ ያውቃታል
ዘርዋ ፡ ሳይታወቅ ፡ እንዴት ፡ ያገባታል ።
እስዋን ፡ አያገባም ፡ ሌላ ፡ እድረዋለሁ ፡
የመኳንንት ፡ ልጅ ፡ አጭቸለታለሁ ።
እሱም ፡ ተናገረ ፡ ሌላም ፡ አላገባ ፡
ስጡኝ ፡ ጠመንጃዬን ፡ ጭራ'ሽ ፡ ውድማ ፡ ልግባ ።
አባቱም ፡ መለሰ ፡ ከወደዳት ፡ ሆድህ ፡
አግብተህ ፡ ተቀመጥ ፡ ሁን ፡ እንደፈቃድህ ።
ወዲያውም ፡ ለእናቱ ፡ ነገሩን ፡ አጫውተው ፡
የማይቀር ፡ መሆኑን ፡ ገልጸው ፡ አስረድተው ፡
ድግሱን ፡ ጀመሩ ፣ ሁሉን ፡ አዘጋጅተው ።
እንደዚሁም ፡ ደግሞ ፡ ድግሱ ፡ ሲደርስ ፡
በልኳ ፡ አሰፍተው ፡ የሐር ፡ ቀሚስ ፡
ኩታም ፡ አሠሩና ፡ ሰጥዋት ፡ እንድትለብስ ።
ሠርጉም ፡ ጥሩ ፡ ነበር ፡ ከልክ ፡ የተረፈ ፡
ያለቅጥ ፡ ያማረ ፡ ከመጠን ፡ ያለፈ ።
የሠርጋቸውም ፡ ቀን ፡ ሲቀረው ፡ ጥቂት ፡
አዘጋጅተውላት ፡ የሙሽራ ፡ ቤት ፡
አብረው ፡ የነበሩት ፡ ሆነው ፡ ባንድነት ፡
ልጆችም ፡ ነበሩ ፡ ካለችበት ፡ ቤት ፡
እስዋም ፡ ተናገረች ፡ እንዲህ ፡ በማለት ።
እንግዲህ ፡ አደራ ፡ በሰማይ ፡ በምድር ፡
አትናገሩብኝ ፡ ይኸንን ፡ ነገር ።
ብላ ፡ ወዲያውኑ ፡ ተናግራ ፡ ይህን
አባቷ ፡ ልጅ ፡ ሁና ፡ ያሰፋላትን ፡
በወርቅ ፡ የነደደ ፡ ሐር ፡ ቀሚሷን ።
ይዛ ፡ ነበረና ፡ በጨርቅ ፡ ጠቅልላ ፡
አውጥታ ፡ ለበሰች ፡ ይግረማቸው ፡ ብላ ።

ተሞሽረችና ፡ ብቅ ፡ ብትል ፡ ለብሳ ፡
ቤት ፡ የተቃጠለ ፡ እሳት ፡ የተነሣ ።
ይኸ ፡ ሐር ፡ ቀሚስ ፡ ከቅላቷ ፡ ጋራ ፡
አስመሰለው ፡ ቤቱን ፡ ኤሌትሪክ ፡ የበራ ።
ይገረም ፡ ነበረ ፡ በመላው ፡ ፍጥረት ፡
እንደዚህ ፡ ያማረች ፡ የሆነች ፡ ውበት ።
አላየንም ፡ እኛ ፡ ከቶ ፡ ባለም ፡ ላይ ፡
ቅላቷ ፡ የሚያበራ ፡ እንደ ፡ ቀን ፡ ፀሐይ ።
እያሉ ፡ ያስቡ ፡ ነበር ፡ በልባቸው ፡
የዚች ፡ የልጅ ፡ ፍጥረት ፡ እየገረማቸው ።
በታላቅ ፡ ደስታ ፡ ሠርጉም ፡ አለፈና ፡
ወንድ ፡ ልጅ ፡ ወለደች ፡ ዓመት ፡ ቆየችና ።
ደግሞ ፡ ቆየችና ፡ አንድ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡
አሁንም ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ወለደችለት ፡
በጣም ፡ የተዋበ ፡ የቆነጀ ፡ ውበት ።
ወዲያው ፡ ቆየችና ፡ እናትና ፡ አባቴን ፡
እባክህ ፡ አሳየኝ ፡ እንሂድ ፡ አብረን ፡
ብላ ፡ ጠየቀችው ፡ በማስተዛዘን ።
እሱም ፡ መለሰላት ፡ ከሆዱ ፡ በውነት ፡
እሽ ፡ ምንቸገረኝ ፡ እንሄዳለን ፡
እናትና ፡ አባቴ ፡ ከፈቀዱልን ።
ወዲያውም ፡ ለአባቱ ፡ ሄዶ ፡ ቢነግራቸው ፡
አይቻልም ፡ አሉት ፡ ጨክኖ ፡ ሆዳቸው ።
ቡዳ ፡ ትሁን ፡ ጠይብ ፡ ሳታውቅ ፡ አግብተህ ፡
ደግሞ፡አብረሃት ስትሄድ ብትቀርብኝ ወድቀህ
ብለው ፡ ከለከሉት ፡ ጨክነው ፡ አባቱ ፡
እሱም ፡ እያዘነ ፡ ይኽን ፡ በመስማቱ ፡
ሄደና ፡ ነገራት ፡ ለመልካሟ ፡ ሚስቱ ፡

እሷም ፡ በጣም ፡ አዝና ፡ በኚሁ ፡ ባባቱ ።
ምን ፡ ይሻላል ፡ ታዲያ ፡ አለችው ፡ መልሳ ፡
እያስተዛዘነች ፡ ቃሏን ፡ አለስልሳ ፡
ስለጠየቀችው ፡ መልሳ ፡ መልሳ ።
አንቺ ፡ በፊት ፡ ሂደሽ ፡ አባትሽን ፡ አይተሽ ፡
አትቆይ ፡ በፍጥነት ፡ ቶሎ ፡ ተመለሽ ፡
አብረን ፡ እንሄዳለን ፡ ቆይተን ፡ ትንሽ ።
ብሎ ፡ ወታደሮች ፡ አሽከር ፡ አስከትሎ ፡
በጣም ፡ የሚያምነውን ፡ ደጃዝማች ፡ ጨምሮ ።
የሚቀጥለውን ፡ አደራ ፡ ጭምር ፡
አደራ ፡ በሰማይ ፡ አደራ ፡ በምድር ፡
የልጆቼንና ፡ የሚስቴን ፡ ነገር ።
አደራዬን ፡ ሁሉ ፡ ባንተ ፡ ላይ ፡ ጥያለሁ ፡
እንደ ፡ መድኃኔ ፡ ዓለም ፡ አንተን ፡ አምኛለሁ ።
ብሎ ፡ ለመነና ፡ አጥብቆ ፡ በብርቱ ፡
ሚስቱን ፡ ተሰናብቶ ፡ ቀረ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ።
እሷም ፡ ስትሄድ ፡ ውላ ፡ ታጅባ ፡ ባሽከር ፡
ቀኑ ፡ ስለመሸ ፡ ብለው ፡ እንደር ፡
ድንኳን ፡ ተከሉና ፡ እልም ፡ ባለ ፡ ዱር ፡
ዙሪያውን ፡ ዘብ ፡ ቆሞ ፡ ብዙ ፡ ወታደር ።
አልጋ ፡ ተነጥፎላት ፡ በድንኳኑ ፡ ውስጥ ፡
ልጆቿን ፡ ታቅፋ ፡ ተኝታ ፡ ጥቂት ፡
ደጃዝማቹ ፡ ገብቶ ፡ እንደዚህ ፡ አላት ።
ያሉትን ፡ አይነሳ ፡ መቸም ፡ እግዚአብሔር ፡
እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ሳስብሽ ፡ ስኖር ፡
አገናኝን ፡ ዛሬ ፡ ወይ ፡ ያምላክ ፡ ነገር ፡
እንግዲህ ፡ እኅቴ ፡ አብረን ፡ እንደር ፡
ልጆችሽ ፡ ይውረዱ ፡ ይተኙ ፡ ከምድር ፡

እንተኛ ፡ አንችና ፡ እኔ ፡ በመፈቃቀር ።
እሷም ፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ በብዙ ፡ ደንግጣ ፡
ካንተ ፡ ጋር ፡ አልተኛም ፡ ነፍሴ ፡ ብትወጣ ።
ባሌም ፡ አንተን ፡ አምኖ ፡ አደራ ፡ሲልህ ፡
አዝናለሁ ፡ በውነቱ ፡ በመዘንጋትህ ፡
እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ በመናገርህ ።
እሱም ፡ መለሰላት ፡ እንተኛ ፡ ይልቁን ፡
ልጅሽን ፡ አርደዋለሁ ፡ ይኸንን ፡ ትልቁን ።
ሆድህ ፡ ከጨከነ ፡ እረደው ፡ እፊቴ ፡
ካንተ ፡ ጋር ፡ አልተኛም ፡ ሳለሁ ፡ በሕይወቴ ፡
ቆንትም ፡ እንደዚሁ ፡ በሕፃንነቴ ፡
ስለይ ፡ ጨክኜ ፡ ከእናቴ ፡ ካባቴ ።
በዚሁ ፡ ነገር ፡ ነው ፡ ስወጣ ፡ ከቤቴ ።
እሱም ፡ ጨከነና ፡ እምቢ ፡ በማለቷ ፡
ልጅዋን ፡ አረደባት ፡ ወስዶ ፡ ከደረቷ ፡
ደግሞ ፡ እሬሳውንም ፡ ዘረጋው ፡ እፊቷ ።
ስታለቅስ ፡ አድራ ፡ ሲነጋ ፡ ሌሊቱ ፡
ጉዞዋቸውን ፡ ያዙ ፡ ደግሞ ፡እንደ፡ ትላንቱ ።
ሲሄዱ ፡ ዋሉና ፡ ስለመሸ ፡ ቀኑ ፡
እንደር ፡ አሉና ፡ ድንኳኑን ፡ ተከሉ ።
ወዲያው ፡ ሰዓት ፡ ሲደርስ ፡ ጊዜ ፡ የመኝታ ፡
አላት ፡ እንተኛ ፡ በፈጠረሽ ፡ ጌታ ።
ይህንን ፡ ስትሰማ ፡ እንዲህ ፡ አለችው ፡
ከኔ ፡ ጋር ፡ መኝታ ፡ ፍጹም ፡ ዘበት ፡ ነው ፡
ልብህም ፡ ማሰቡ ፡ በውነት ፡ ጨካኝ ፡ ነው ።
እሱም ፡ መለሰና ፡ እንደዚህ ፡ አላት ።
በጭካኔ ፡ ሆዱ ፡ እያስፈራራት ።
ትናንት ፡ አረድኩብሽ ፡ ትልቁን ፡ ልጅሽን ፡

ዛሬ ፡ ልደግመው ፡ ነው፡ ደግሞ ፡ ትንሹን ።
እሷም ፡ ተናገረች ፡ እንደፈቀደህ ፡
ካልሳሳህ ፡ እረደው ፡ ከፀና ፡ ሆድህ ፡
ከኔ ፡ ጋር ፡ መኝታ ፡ አያስብ ፡ ልብህ ።
እስኪወጣ ፡ ነፍሴ ፡ አፈር ፡ እስክሆን ፡
ካንተ ፡ ጋር ፡ አልተኛም፡ከቶ፡ምን፡ ቢሆን ።
ወንድሜ ፡ ልንገርህ ፡ የሆዴን ፡ በውነት ፡
በጭራሽ ፡ አታስብ ፡ ከኔ ፡ ለመኛት ፡
በሕይወቴ ፡ ሳለሁ ፡ ለመገናኘት ።
አንተ፡አብደህ፡እንደሆን፡ አላበድኩም፡እኔ፡
በጣም ፡ እፈራለሁ ፡ በሰማይ ፡ ኵነኔ ።
ይህንን ፡ ሲሰማ ፡ በጨከነ ፡ ሆዱ ፡
ልጅዋን፡አርዶ፡ጣለው፡ደግሞ፡እንደ ልማዱ
ሌሊቱም ፡ ሲነጋ ፡ ተነሥተው ፡ ሲሄዱ ፡
ቀኑ ፡ ስለመሸ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ልማዱ ።
ተቀምጠው ፡ ሳለ ፡ ድንኳን ፡ አስተክለው ፡
ይጠይቃት ፡ ነበር ፡ እንደሚቀጥለው ።
ከትላንት ፡ ወዲያና ፡ ትላንትና ፡ ማታ ፡
ልጆችሽ ፡ ታረዱ ፡ ያለሐዘኔታ ፡
ዛሬ ፡ አብረን ፡ እንደር ፡ በፈጠረሽ ፡ ጌታ ፡
እሷም ፡ ተናገረች ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ መኝታ ፡
ልብህ ፡ እንዳያስብ ፡ ትላንትና ፡ ማታ ፡
አጫውቼሃለሁ ፡ ሁሉን ፡ በዝግታ ፡
የሆዴን ፡ ዘርዝሬ ፡ ሳልቸኩል ፡ በርጋታ ።
ምን ፡ ያደርግልሀል ፡ በከንቱ ፡ ምኞት ፡
የሕልም ፡ እንጀራ ፡ ነው ፡ ከኔ፡ጋር፡መኛት።
ለምን ፡ አይገባህም ፡ ሰው ፡ የሚነግርህ
መልሰህ ፡ ቀልሰህ ፡ ትጠይቃለህ ፡
አልገባህ ፡ እንደሆን ፡ ደግሞ ፡ ልንገርህ ፡

ከኔ ፡ ጋር ፡ ለመኖት ፡ አያስብ ፡ ልብህ
ልጆቼን ፡ አርዶሐል ፡ ደግሞ ፡ ምን ፡ ቀረህ ፡
አንተ ፡ በውነተኛው ፡ አረመኔ ፡ ነህ ፡
እንደዚያ ፡ ለምኖ ፡ አደራ ፡ ሲልህ ፡
ምን ፡ አደራ ፡ በላ ፡ ጨካኙ ፡ ሰው ፡ ነህ ፡
ከሰዎቹ ፡ ሁሉ ፡ አንተ ፡ ተመርጠህ ፡
ለዚሁ ፡ ነበር ፡ ወይ ፡ አደራ ፡ ያለህ ፡
ምንኛ ፡ ጨካኝ ፡ ነው ፡ ከቶ ፡ ልቦናህ ፡
እንደምን ፡ ቢጠና ፡ ቢጨክን ፡ ሆድህ ፡
ለእንዲህ ፡ ያለው ፡ ነገር ፡ ሰው ፡ ትገድላለህ ።
እሱም ፡ መለሰላት ፡ ውድ ፡ እህቴ ፡ ሆይ ፡
እግዜር ፡ ቢኰንናት ፡ ነፍሴን ፡ በሰማይ ፡
ካንቺ ፡ ጋር ፡ መኘታ ፡ ጽድቅ ፡ አይደለም ፡ ወይ ።
ላጠፋሁት ፡ ሁሉ ፡ ንስሐ ፡ እገባለሁ ፡
ዛሬ ፡ ግን ፡ ካንቺ ፡ ጋር ፡ ላድር ፡ ቆርጫለሁ ፡
እምቢ ፡ ብትይኝም ፡ ላርድሽ ፡ ታጥቄአለሁ ፡
ከኔ ፡ ጋር ፡ በፍቅር ፡ አብረሽ ፡ ከምታድሪ ፡
ምረጭ ፡ ከነፍስሽ ፡ ታርደሽ ፡ ከምትቀሪ ፡
በውነቱ ፡ ከመጣህ ፡ ጨክነህ ፡ በራሴ ፡
አብረን ፡ እናድራለን ፡ አይብስም ፡ ከነፍሴ ።
አደራ ፡ ከማጉደል ፡ እርኩስ ፡ ከመሆን ፡
ቢቀር ፡ ይሻል ፡ ነበር ፡ እንደኔ ፡ ቢሆን ።
የማይቀር ፡ ከሆነ ፡ ከቶ ፡ ያሰብከው ፡
የቆሙትን ፡ ዘቦች ፡ ትእዛዝ ፡ ስጣቸው ፡
አማን ፡ ነው ፡ አገሩ ፡ ተኙ ፡ በላቸው ።
እሱም ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ እውነቷን ፡ መስሎት
ዘቦቹን ፡ ሰብስቦ ፡ ሁሉን ፡ ባንድነት ፡
ይሰብካቸው ፡ ጀመር ፡ እንዲህ ፡ ብማለት ።

ተኙ ፡ ሁላችሁም ፡ እንደፈቃዳችሁ ፡
አማን ፡ ነው ፡ አገሩ ፡ አያስብ ፡ ልባችሁ ፡
በጭራሽ ፡ አትፍሩ ፡ አይሥጋ ፡ ሆዳችሁ።
እያለ ፡ ሲናገር ፡ ይኸ ፡ ደጃዝማች ፡
ልጅቷ፡ባንድ፡ወገን ፡ ጠፍታ፡ አመለጠች ።
ወዲያው ፡ ተመልሶ ፡ ሊተኛ ፡ ቢመጣ
ባዶ፡ ድንኳን፡ እንጅ ፡በውስጡ፡ ሰው ፡አጣ ፡
ያለቅጥ ፡ ደንግጦ ፡ ቢገባ ፡ ቢወጣ ፡
ቢጨነቅ ፡ ቢፈልግ ፡ ቢነድ ፡ ቢቆጣ ፡
አንድ ፡ ጊዜ ፡ ሄዳ ፡ ከየት፡አገር ፡ ትምጣ ።
ዘቦቹን ፡ ጠራና ፡ እውነት ፡ አስመስሎ ፡
ይናገር ፡ ጀመረ ፡ እንዲህ ፡ አሳምሮ ።
አባቱ ፡ ሲቆጡት ፡ ሲመክሩት ፡ ጥንቱን ፡
ቡዳ ፡ ትሁን ፡ ጠይብ ፡ ሳታውቅ ፡ ዘርዋን ፡
እንዴት ፡ ታገባለህ ፡ ሲሉት ፡ ዱሮውን ፡
እምቢ ፡ ብሎ ፡ አግብቶ ፡ በራሱ ፡ ሥልጣን፡
ሽማግሌ ፡ ያለው ፡ አይቀር ፡ ምን ፡ ቢሆን ፡
ሁለቱን ፡ ልጆቿን ፡ በላች ፡ ሰሞኑን ፡
የምትበላው ፡ አጥታ ፡ ጠፋች ፡ ጭራሹን፡
እንሂድ ፡ ተነሱ ፡ ወደ ፡ ቤታችን ፡
እንደዚሁ ፡ ገልጸን ፡ እንናገራለን ፡
ብሎ ፡ ሰበከና ፡ ጨረሰ ፡ ውሸቱን ፡
ጉዞአቸውን ፡ ያዙ ፡ ነቅለው ፡ ድንኳኑን ።
ሲጓዙ ፡ ሰንብተው ፡ ሲደርሱ ፡ ከቤት ፡
ለባሏ ፡ ነገረው ፡ እንዲህ ፡ በማለት ፡
ሐሰቱን ፡ በሙሉ ፡ አስመስሎ ፡ እውነት ፡
ለካስ ፡ ቡዳ ፡ ኖራ ፡ ያንተ ፡ ባለቤት ።
ሁለቱን ፡ ልጆቿን ፡ ሰሞነን ፡ በላች ፡

ደግሞ ፡ በማግስቱ ፡ እራሷ ፡ ጠፉች ፡
እንደዱር ፡ አራዊት ፡ ከጫካ ፡ ገባች ።
ባሏም ፡ ይኸን ፡ ሰምቶ ፡ በጣም ፡ አዘነና ፡
ልብሱን ፡ ሁሉ ፡ አውልቆ ፡ ከል ፡ ነከረና ፡
ባዘን ፡ ተጨበጠ ፡ እውነት ፡ ነው ፡ አለና ፡
ምነው ፡ በቀረብኝ ፡ ካንች ፡ መጋባቴ ፡
እንደከለከሉኝ ፡ እናትና ፡ አባቴ ።
በቀረብኝ ፡ ኖሮ ፡ ዓይኔ ፡ ባላየሽ ፡
የሕይወቴ ፡ ጌታ ፡ አለኝታዬ ፡ ነሽ ።
ይገባኛል ፡ ማልቀስ ፡ ይገባኛል ፡ ማዘን ፡
አበባዋ ፡ ሚስቴ ፡ ሆንሽብኝ ፡ ሰቀቀን ፡
እምን፡ቦታ፡ገብተሽ ወዴት፡ወድቀሽ ይሆን፧
ይመጣል፡በሕልሜ ፡ ዓይንና ፡ ጥርስሽ ፡
ዳግም ፡ ትሕትናሽ ፡ የቁም ፡ ነገርሽ ።
አይጠፉም ፡ ከሆዴ ፡ ከቶ ፡ ምን ፡ ቢሆን ፡
እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡ ያንች ፡ ሰቀቀን ።
ወይ ፡ እኔ ፡ ዘንድሮ ፡ ምነው ፡ በዛ ፡ ጉዴ ፡
አንጀቴ ፡ ነደደ ፡ ተቃጠለ ፡ ሆዴ ።
አወይ፡የአምላክ፡ቁጣ፡አወይ፡የእግዜር፡ቁጣ
ምነው ፡ በቀረብኝ ፡ ከቤቴ ፡ ሳትወጣ ፡
ልጆቼ ፡ ሳይሞቱ ፡ እሷንም ፡ ሳላጣ ።
እንደዚህ ፡ እያለ ፡ ሲጨነቅ ፡ በብዙ ፡
ቀይ ፡ የነበረው ፡ ልጅ ፡ ጥቁር፡ሆነ ፡ ወዙ።
ወዲያውም ፡ ያች ፡ ልጅ፡ጠፍታ፡ ስትሄድ ፡
አንድ ፡ ሽማግሌ ፡ ቆመው ፡ ከመንገድ ፡
እየተገረሙ ፡ በዚች ፡ በልጅ ፡ ጉድ ፡
ያደንቁ ፡ ነበረ ፡ እያሉ ፡ ወይጉድ ።
ያች ፡ ልጅ፡ቆንጆ ፡ ነች ፡ እንደ፡መላእክት፡

በልሜ ፡ ነው ፡ በውኔ ፡ አሁን ፡ የማያት ።
ወደኔ ፡ ብትመጣ ፡ እጅ ፡ ብትነሳኝ ፡
እንዴት ፡ ዋሉ ፡ ብላ ፡ ብታ ናግረኝ ።
ሰላምታ ፡ ብትሰጠኝ ፡ ተናግራ ፡ እንደሰው ፡
ንብረቴን ፡ በሙሉ ፡ በወሰዳችው ፡
እያሉ ፡ ሲያስቡ ፡ በልቡናቸው ፡
ልጅቷ ፡ ተጠጋች ፡ አጠገባቸው ፡
እጅ ፡ ነሳቻቸው ፡ ቀርባ ፡ እፊታቸው ።
እሳቸውም ፡ አሏት ፡ እንዴት ፡ ዋልሽ ፡ እኅቴ
በልሜ ፡ ነው ፡ በውኔ ፡ የቆምሽው ፡ እፊቴ ፡
እባክሽ ፡ ንገሪኝ ፡ አንቺ ፡ ልጅ ፡ በሞቴ ።
ከየት ፡ አገር ፡ መጣሽ ፡ አትደብቂኝ ፡
እባክሽ ፡ ንገሪኝ ፡ አታስጨንቂኝ ።
እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ስኖር ፡ ባለም ፡ ላይ ፡
እንዳንች ፡ ያለ ፡ ቆንጆ ፡ አላሁኝ ፡ ሳላይ ፡
ከፀጉርሽ ፡ የሽንጥሽ ፡ ከዓይንሽ ፡ የጥርስሽ ፡
ደግሞ ፡ ያካሄድሽ ፡ ያረማመድሽ ።
እንዲሁም ፡ ንገሪኝ ፡ የምታስቢውን ፡
እኔ ፡ እሰጥሻለሁ ፡ የምትፈልጊውን ፡
ልጅቷም ፡ መለሰች ፡ የምፈልገውን ፡
ከሰጡኝ ፡ በሙሉ ፡ ልቤ ፡ ያሰበውን ፡
ያውልቁና ፡ ይስጡኝ ፡ ሱሪና ፡ ኮትዎን ።
እኛም ፡ ሽማግሌ ፡ ገረማቸውና ፡
ሱሪና ፡ እጀጠባብ ፡ ከቤት ፡ አመጡና ፡
ያውልሽ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፡ ውሰጂው ፡ አሉና ፡
ሰጡዋት ፡ ለልጅቷ ፡ በጣም ፡ አዘኑና ፡
እሷም ፡ ተቀብላ ፡ በታላቅ ፡ ምሥጋና ፡
የሐር ፡ ቀሚሷን ፡ አወለቀችና ፡

እንደወንድ ፡ ሱሪ ፡ ኮት ፡ ለበሰችና ፡
ጉዞዋን ፡ ቀጠለች ፡ በታላቅ ፡ ጐዳና ።
ስትሄድ ፡ ቆይታ ፡ በዚያው ፡ በመንገድ ፡
አንድ ፡ ሰው ፡ አገኘች ፡ ዕቃ ፡ ሲነግድ ።
ብላ ፡ ጠየቀችው ፡ አሳድረኝ ፡ ዛሬ ፡
ዘመዶችም ፡ የሉኝ ፡ እሩቅ ፡ ነው ፡ አገሬ ፡
ስገሠግሥ ፡ መጣሁ ፡ እንደመራኝ ፡ እግሬ ፡
እንዳላሜውትህ ፡ ብዙ ፡ ነው ፡ ታምሬ ።
እሱም ፡ መለሰና ፡ እንደዚህ ፡ አላት ፡
ያውም ፡ እየማለ ፡ ከሆዱ ፡ በውነት ።
እዚህ ፡ ተቀምጬ ፡ የምነግደው ፡
ወድጄን ፡ አይደለም ፡ ተቸግሬ ፡ ነው ፡
ምሣዬ ፡ አንድ ፡ እንጀራ ፡ ራቴም፡ያው ፡ ነው ፡
ደግሞ ፡ እኔ ፡ ቤት ፡ አድረህ፡ምን፡ልትበላ፡ነው
ልጅቷም ፡ መለሰች ፡ ምንም ፡ አልፈልግ ፡
ተጠግቼ ፡ ልደር ፡ ከዚህ ፡ ከቤት ፡ ጥግ ።
እሱም ፡ ተናገረ ፡ ላንድ ፡ ቀን ፡ አዳር ፡
በል ፡ ጠጋ ፡ በልና ፡ ተኝተህ ፡ እደር ።
ወዲያውም ፡ ሲበላ ፡ አምጥቶ ፡ እራቱን ፡
ያንን ፡ አንድ ፡ እንጀራ ፡ በፊት ፡ ያለውን ፡
ቆረሰና ፡ ሰጣት ፡ ለእሷ ፡ ግማሹን ።
እዚያው ፡ አደሩና ፡ ሲነጋ ፡ ሌሊቱ ፡
ትሄዳለች ፡ ብሎ ፡ ሲአያት ፡ ባለቤቱ ።
ጭራሽ ፡ ጠየቀችው ፡ እንደዚህ ፡ ስትል ፡
እባክህ ፡ ጌታዬ ፡ ካንተ ፡ ጋር ፡ ልሁን ።
እሱም ፡ መለሰላት ፡ ምን ፡ ልትሰራልኝ ፡
ለእኔውም ፡ ለራሴ ፡ በቂ ፡ ንግድ ፡ የለኝ ፡
ዛሬን ፡ ባሳድርህ ፡ እንድታጸድቀኝ ።
ልጅቷም ፡ መለሰች ፡ ጌታዬ ፡ ግድ ፡ የለም ፡

ወይ፡ትክብር፡ይሆናል፡ሰው፡እንዳይሆን፡የለም፡
አንተም ፡ አባቴ ፡ ነህ ፡ ልጅህ ፡ ነኝ ፡ እኔም ፡
ካለሁ ፡ በሕይወቴ ፡ ካንተ ፡ አልለይም ።
ሰውዬውም ፡ አላት ፡ ከኔ ፡ ለመኖር ፡
ፈቃድህ ፡ ከሆነ ፡ እንሁን ፡ አብረን ፡
በል ፡ ተቀመጥና ፡ የሆነው ፡ ይሁን ፡
እንነግዳለን ፡ ገዝተን ፡ ምናምን ።
ብሎ ፡ በማለስለስ ፡ ስለነገራት ፡
እጅግ ፡ ያለመጥን ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ አላት ፡
ይነግዱ ፡ ጀመር ፡ ሻይና ፡ ብስኩት ፡
ወዲያውም፡ሰንብተው፡ቆይተው ፡ ጥቂት ፡
ብዙ ፡ ትርፍ፡ አገኑ ፡ በሀብት ፡ ላይ ፡ ሀብት ።
እንዲህ ፡ ሲነግዱ ፡ እስከ ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡
በሀብት ፡ በገንዘብ ፡ በለጡ ፡ ከንጉሥ ።
ልጅቷም ፡ አለችው ፡ እናሠራ ፡ ቤት ፡
ይኸን ፡ ሁሉ ፡ ገንዘብ ፡ የምንከትበት ፡
ድግሥ ፡ እንደግሥ ፡ ብዙ ፡ ብዙ ፡ ዓይነት ፡
ከግራና ፡ ከቀኝ ፡ እንጥራ ፡ መንግሥት ፡
እንድንተዋወቅ ፡ ብዙ ፡ መኳንንት ።
እሱም ፡ መለሰላት ፡ እሺ ፡ የኔ ፡ ልጅ ፡
ብታስተዋውቀኝ ፡ ከብዙ ፡ ወዳጅ ፡
እንዴት ፡ እጠላለሁ ፡ እወዳለሁ ፡ እንጅ ።
ወዲያው ፡ ተደግሦ ፡ ቤት ፡ ሙሉ ፡ ድግሥ፡
ከግራና ፡ ከቀኝ ፡ ተጠራ ፡ ንጉሥ ።
እነዚህ ፡ ንጉሦች ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ ያሉት ፡
አንዱ ፡ የባሏ፡ አባት፡ አንዱም፡ የሷ ፡ አባት፡
ተጠርተው ፡ ሲመጡ ፡ ከዚያ ፡ ከሰው ፡ ቤት፡
አብረውም ፡ ነበሩ ፡ ብዙ ፡ መኳንንት ፡

ደጃዝማች ፡ ቀኛዝማች ፡ ብዙ ፡ ሠራዊት፡
እንተኛሽ ፡ ያኋትም ፡ ጥንት ፡ አባቷ፡ቤት፡
ቄሱም ፡ ደጃዝማቹም ፡ ነበሩ ፡ አንድነት ።
ደግሞ ፡ ልጆቿንም ፡ አርዶ ፡ የጣላቸው ፡
ተቀምጠ ፡ ነበር ፡ አንድነት፡አብሮዋቸው ፡
የመጡት ፡ በሙሉ ፡ እንደሚገባቸው ፡
ተጋብዘው ፡ ሲያበቁ ፡ በየበኩላቸው ።
እንደዚህ ፡ አለችው ፡ ልጅቷም ፡ እሱን ፡
ከተጋበዙልን ፡ እንግዶቻችን፡
እንግዲህ ፡ በላቸው ፡ ትንሽ ፡ አጫውቱን።
እነሱም ፡ አናውቅም ፡ ቢሉህ ፡ምናልባት፡
በያይነቱ ፡ ያውቃል ፡ የእኔ፡ልጅ ፡ ተረት ።
ነገር ፡ ግን ፡ ሲጫወት ፡ እሱ ፡ ተረቱን ፡
የሚያቋርጠው ፡ ሰው ፡ያንን፡ ጨዋታውን፡
ሺህ ፡ ብር፡ እንዲከፍል፡ያጠብቃል፡ውሉን፡
ብለህ ፡ ንገራቸው ፡ ዘርዝረህ ፡ ሁሉን ።
እሱም ፡ እሺ ፡ ብሎ ፡ ሄዶ ፡ ነገራቸው ፡
እስኪ፡ ትንሽ፡ተረት ፡አጫውቱን፡አላቸው።
እነሱም ፡ መለሱ፡አንተ፡አጫውተን፡እንጅ ፡
ካንተ ፡ በጣም ፡ እኛ ፡ እንሆናለን ፡ ልጅ ።
ጨዋታ ፡ የሚያውቀው ፡የዱሮ ፡ሰው ፡ ነው ፡
አሁንም ፡ እራስህ ፡ አጫውተን፡አንተው ።
እሱም ፡ ተናገረ ፡ እናንተ ፡ ስሙ ፡ እንጅ ፡
በያይነቱ ፡ ተረት ፡ ያውቃል ፡ የኔ ፡ ልጅ ።
ነገር ፡ ግን ፡ ሲተርት ፡ እሱ ፡ ሲጫወት ፡
የተናገረ ፡ ሰው ፡ ባንድ ፡ ምክንያት ፡
ሺህ ፡ ብር ፡ ይቀጣዋል፡ የለውም፡ምሕረት ።
በማለት ፡ ተናግሮ ፡ ልጅቷን ፡ ጠራና ፡

በል ፡ ተጫወት ፡ አላት ፡ በሩን ፡ አዘጋና ።
እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ሲኖሩ ፡ አንድነት ፡
ብሎ ፡ አልጠረጠረም ፡ ከቶ ፡ ሴት፡ልጅ፡ ናት
ልጅቷም ፡ ቀጠለች ፡ በሰው ፡ አስመስላ ፡
ትናገር ፡ ጀመረ ፡ ታሪኩን ፡ ዘርዝራ ፡
የደረሰባትን ፡ ያን ፡ ሁሉ ፡ መከራ ፡
እንደዚ.ህ ፡ ብላ ፡ ነው ፡ ዳግም ፡ ስታወራ ።

## አ ን ባ ቢ ፡ ሆ ይ ።

እዚህ ፡ ላይ ፡ ቃሉ ፡ ስለተደጋገመ ፡ ሳት ሰለች ፡ ፍሬ ፡ ነገሩን ፡ እስከ ፡ መጨረሻው ፡ ተመልከት ።

## አበባዬ ፡ ፍቅሬ ።

አንድ ፡ ንጉሥ ፡ ወልዶ ፡ ሁለት ፡ ልጆች ፡
አንድ ፡ ወንድ ፡ አንድ፡ሴት፡ቆንጆ፡ቆንጆዎች ፡
እንዲሁም ፡ ሴቷ ፡ ልጅ ፡ በጣም ፡ ቀይ ፡ ነች ፡
እንደ ፡ አልማዝ ፡ እንደ፡ወርቅ፡ያብረቀረቀች ፡
ፍጥረት ፡ የቀናባት ፡ ውበት ፡ የሆነች ፡
እንደ ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ፡ የለሰለሰች ።
እጅግ ፡ ያለመጠን ፡ አባቷ ፡ ወዷት ፡
ከፍተኛ ፡ ፎቅ ፡ ቤት ፡ አሠርቶላት ፡
የቄስ ፡ አስተማሪ ፡ ቀጥሮ ፡ አምጥቶላት ፡
እንድትማርለት ፡ መልካሙን ፡ ትምህርት ፡
እያበረታታ ፡ ማታና ፡ ጠዋት ፡
አይዞሽ ፡ በርቺ ፡ ልጄ ፡ ጠንክሪ ፡ እያላት ፡
ወደ ፡ መንገድ ፡ ሲሄድ ፡ ተነሥቶ ፡ ድንገት ፡
እስከመጣ ፡ ድረስ ፡ ከምሄድበት ፡
እንዳትቦዝኚ ፡ ለያዝሽው ፡ ትምህርት ፡
እመጣለሁና ፡ ቶሎ ፡ በፍጥነት ።
አይዞሽ ፡ የኔ ፡ አበባ ፡ ቅርም ፡ አይበልሽ ፡
ፈጥነን ፡ እንመጣለን ፡ እኔና ፡ እናትሽ ፡
ቄሱም ፡ ደህና ፡ ሰው፡ነው፡ያንቺ፡አስተማሪሽ ፡
እነግርልሻለሁ ፡ እንዲያስተምርሽ ፡
በጣም ፡ እንዲያስጠናሽ ፡ እንዲገልጽልሽ ፡
ደጃዝማችም ፡ አለ ፡ ቅርም ፡ አይበልሽ ፡
ጭራሽ ፡ አታስቢ ፡ አይፍራ ፡ ሆድሽ ፡
እንዳትባልጊ ፡ ሰው ፡ እንዳይሰድብሽ ፡
በጣም ፡ አጥብቄ ፡ ነው ፡ አደራ ፡ ስልሽ ።
ቄሱንም ፡ ሄደና ፡ የልጄን ፡ ነገር ፡

አደራ ፡ በሰማይ ፡ አደራ ፡ በምድር ፡
እንድትማር ፡ ይሁን ፡ እንድትጠነክር ።
ደጃዝንማቹ ፡ ደግሞ ፡ እንግዲህ ፡ አደራ ፡
ልጄን ፡ ጠብቅልኝ ፡ ከመምሕሩ ፡ ጋራ ።
ባንተ ፡ ላይ ፡ ጥያለሁ ፡ አደራ ፡ የቤቴን ፡
የትዳሬን ፡ ነገር ፡ የመላ ፡ ንብረቴን ።
እኔ ፡ መሄዴ ፡ ነው ፡ ለብርቱ ፡ ነገር ፡
ድንገት ፡ ተነስቼ ፡ ወደውጪ ፡ አገር ፡
አደራ ፡ ጥያለሁ ፡ በሰማይ ፡ በምድር ፡
እንዳልሰማ ፡ ክፉ ፡ የልጄን ፡ ነገር ።
ብሎ ፡ ወዲያውኑ ፡ ጉዞውን ፡ ቀጠለ ፡
ቁሱም ፡ ያለመጠን ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ ዋለ ፡
ወዲያውም ፡ ጠየቃት ፡ እንደዚህ ፡ እያለ ።
አብረን ፡ እንተኛ ፡ ቆንጆት ፡ እባክሽ ፡
ሁሉን ፡ በያይነቱ ፡ እንዳስተምርሽ ፡
ለሰውም ፡ አልነግር ፡ በፍጹም ፡ ጭራሽ ፡
አይዞሽ ፡ ግድ ፡ የለሽም ፡ አይፍራ ፡ ሆድሽ ፡
እንዲህ ፡ ስለምንሽ ፡ እኔን ፡ ታሳፈርሽ ፡
እንኳን ፡ ላስተምርሽ ፡ ዞሬም ፡ አላይሽ ።
ብሎ ፡ ቢጠይቃት ፡ ልጅቱ ፡ ደንግጣ ፡
ታለቅስ ፡ ጀመረች ፡ በመስኮት ፡ ተቀምጣ ።
ደግሞ ፡ ደጃዝማቹ ፡ መጣና ፡ ከቤት ፡
ይለምናት ፡ ጀመር ፡ እንዲህ ፡ በማለት ፡
ብቅ ፡ ብለሽ ፡ ሳይሽ ፡ እኔ ፡ በመስኮት ፡
እደነግጣለሁ ፡ እህቴ ፡ በውነት ፡
አጥብቄ ፡ እመኛለሁ ፡ ማታና ፡ ጠዋት ፡
አንድ ፡ ቀን ፡ ካንቺ ፡ ጋር ፡ ለመገናኘት ፡
እንዳታሳፍሪኝ ፡ ፍቅሬ ፡ የኔ ፡ እኅት ።

ይኸንን ፡ ስትሰማ ፡ አካላቷ ፡ አለቀ ፡
ያስለቅሳት ፡ ጀመር ፡ እያንሰቀሰቀ ።
ቂሱም ፡ ደጃዝማቹም ፡ ደፍረው ፡ ቢናገሯት ፡
ሕይወቷ ፡ ያለፈ ፡ የሞተች ፡ መሰላት ።
ትናደድ ፡ ጀመረ ፡ እነሱን ፡ ስታይ ፡
በፍጹም ፡ መሰሏት ፡ ያባቷ ፡ ገዳይ ።
ወዲያውም ፡ ልጅቷ ፡ መለሰችለት ፡
እያስተዛዘነች ፡ እንዲህ ፡ በማለት ፡
እኔ ፡ ያንተ ፡ ልጅ ፡ ነኝ ፡ አንተ ፡ የኔ ፡ አባት ፡
ፍጹም ፡ አንተና ፡ እኔ ፡ ለመገናኘት ፡
ሆነኔ ፡ ያመጣል ፡ በላይኛው ፡ ቤት ።
አዝናለሁ ፡ በብዙ ፡ ባንተ ፡ በራስህ ፡
እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ በመናገርህ ።
ትልቅ ፡ ሰው ፡ መስለኸኝ ፡ አከብርህ ፡ ነበር ፡
ለካስ ፡ ትንሽ ፡ ልጅ ፡ ነህ ፡ ገና ፡ እምር ፡ ታህል ።
ጥንት ፡ ትልቅ ፡ ነበር ፡ በጣም ፡ እራስህ ፡
እያነሰ ፡ ሄደ ፡ እየቀለለህ ፡
ለአንተ ፡ ባይታይህ ፡ ባይታወቅህ ፡
በግልጽ ፡ ይታየኛል ፡ እኔ ፡ ልንገርህ ።
ይኸንን ፡ ሲሰማ ፡ እየተናደደ ፡
ምንም ፡ ሳይናገር ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ሄደ ፡
ጨሰ ፡ ተቃጠለ ፡ አንጀቱ ፡ ነደደ ፡
እንደሰከረ ፡ ሰው ፡ ጭራሽ ፡ እንዳበደ ፡
ያስኬደው ፡ ጀመረ ፡ እያንገደገደ ።
እንዲሁም ፡ አባቷ ፡ ሆነው ፡ ካሉበት ፡
አልችልህ ፡ ብለውት ፡ የእሷን ፡ ናፍቆት ፡
ልጃቸውን ፡ አሉት ፡ ሄደህ ፡ ጠይቃት ።
ልጁም ፡ እሺ ፡ ብሎ ፡ እየገሠገሠ ፡

ከዚያው ፡ ካለችበት ፡ በፍጥነት ፡ ደረሰ ።
ወዲያው ፡ ተገናኝተው ፡ ከደጃዝማች ፡ ጋራ ፡
ይጠይቀው ፡ ጀመር ፡ ያባቱን ፡ አደራ ።
ደጃዝማችም ፡ አለው ፡ ቤቱ ፡ ደህና ፡ ነው ፡
ልጅቷ ፡ ብቻ ፡ ናት ፡ የባለገችው ፡
በጭራሽ ፡ ግቢውን ፡ ያበላሸችው ፡
ሥራዋ ፡ በሙሉ ፡ የሚያሳዝን ፡ ነው ።
መኳንንቱን ፡ ሁሉ ፡ እየሰደበች ፡
ትልልቁን ፡ ሰዎች ፡ እያዋረደች ፡
ለግድያ ፡ ደርሰው ፡ ብዙ ፡ ጐረምሶች ፡
በጭራሽ ፡ ሽርሙጣ ፡ እብድ ፡ ሆናለች ።
ልጁም ፡ ደነገጠ ፡ ይህን ፡ በመስማት ፡
በውነት ፡ ያደረገች ፡ የሠራች ፡ መስሎት ፡
ተመልሶ ፡ ሄደ ፡ ወደ ፡ መጣበት ።
ላባቱ ፡ ነገረው ፡ ዘርዝሮ ፡ ሁሉን ፡
ወዲያውም ፡ ሲሰማ ፡ አባቷ ፡ ይኸን ።
ልጅየውን ፡ አለው ፡ በቶሎ ፡ ሄደህ ፡
እሷን ፡ እረድና ፡ ሥጋዋን ፡ ቀብረህ ፡
አምጣልኝ ፡ ከደሟ ፡ በጠርሙስ ፡ ቀድተህ ።
ልጁም ፡ እሺ ፡ ብሎ ፡ እንደታዘዘው ፡
ትእዛዙን ፡ ሊፈጽም ፡ አባቱ ፡ እንዳለው ፡
ሲገሰግስ ፡ ሄደ ፡ ደረሰ ፡ ወዲያው ።
ድንገት ፡ ደረሰና ፡ ካለችበት ፡ ቤት ፡
ወዲያው ፡ ተነሽ ፡ ብሎ ፡ ሄደና ፡ ይዟት ፡
እዚያው ፡ አጠገቡ ፡ ቁጭ ፡ በይ ፡ ብሏት ፡
ጉድጓዱን ፡ ሲቆፍር ፡ አርዶ ፡ ሊቀብራት ፡
ስለ ፡ ደከመና ፡ ስለ ፡ አሳዘናት ፡
ትጠይቀው ፡ ጀመር ፡ እንዲህ ፡ በማለት ።
ምነው ፡ የእናቴ ፡ ልጅ ፡ ፍቅሬ ፡ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡

እናትና ፡ አባቴ ፡ ደህናም ፡ አይደሉ ፡ ወይ ።
ወይ ፡ አባቴ ፡ ሞተ ፡ ወይንስ ፡ እናቴ ፡
እባክህ ፡ ንገረኝ ፡ ወንድሜ ፡ በሞቴ ።
ብላ ፡ በማሳዘን ፡ ጋሽዬ ፡ እያለች ፡
ቃሏን ፡ በማለስለስ ፡ እያለቀሰች ፡
ላቡን ፡ በመሐረብ ፡ እየጠረገች ።
መልሳ ፡ ቀልሳ ፡ ስለጠየቀችው ፡
በጣም ፡ ያለመጠን ፡ ስለ ፡ አሳዘነችው ።
እንግዲህ ፡ እህቴ ፡ ልንገርሽ ፡ አላት ፡
የሠራሽው ፡ ሥራ ፡ ባባታችን ፡ ቤት ፡
እየተሳደብሽ ፡ ብዙ ፡ መኳንንት ፡
ሽርሙጥነት ፡ ይዞሽ ፡ ትተሽ ፡ ትምህርት ፡
ይኸን ፡ ነገር ፡ ሰምቶ ፡ ደግሞ ፡ የእኛ ፡ አባት ፡
ተናዶ ፡ ተቃጥሎ ፡ ደርሶ ፡ ለመሞት ፡
እኔንም ፡ አዘዘኝ ፡ እንዲህ ፡ በማለት ።
እሷን ፡ እረድና ፡ ሥጋዋን ፡ ቀብረህ ፡
አምጣልኝ ፡ ከደሟ ፡ በጠርሙስ ፡ ቀድተህ ።
እኔም ፡ ተቆጥቼ ፡ በጣም ፡ ተናድጄ ፡
አባቴ ፡ እንዳዘዘኝ ፡ ልቀብርሽ ፡ አርጄ ፡
ነበር ፡ የመጣሁት ፡ መሞትሽን ፡ ፈቅጄ ።
አሁን ፡ ግን ፡ በለቅሶሽ ፡ ባጠያየቅሽ ፡
እንባሽ ፡ አሳዘነኝ ፡ እንኳንስ ፡ ደምሽ ፡
ብትሞችም ፡ በመንገድ ፡ ጅብም ፡ ቢበላሽ ፡
ቸሩ ፡ መድኃኔ ፡ ዓለም ፡ ባወጣ ፡ ያውጣሽ ፡
ጥፊ ፡ ካጠገቤ ፡ ዓይኔም ፡ አይይሽ ።
ብሎ ፡ እያለቀሰ ፡ ሆዱን ፡ አጥናናና ፡
አንዲት ፡ የበግ ፡ ግልገል ፡ ከቤት ፡ አወጣና ፡
በሰላ ፡ ቢላዎ ፡ እሷን ፡ አረደና ፡

ሬሳውን ፡ ቀብሮ ፡ ከደሟ ፡ ቀዳና ፡
ሰጠው ፡ ለአባትየው ፡ አረድኳት ፡ አለና ።
አባቷም ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ ደሟን ፡ በማየቱ
ወዲያውም ፡ ጠጣና ፡ ነገራት ፡ ለሚስቱ ።
እኔና ፡ አንቺ ፡ ድንገት ፡ ወደዚህ ፡ ብንመጣ
በጣም ፡ ተበላሽታ ፡ ልጃችን ፡ ሸርሙጣ ።
መኳንንቱን ፡ ሁሉ ፡ እየሰደበች ፡
የቤት ፡ አሽከሮቹን ፡ እያዋረደች ፡
ትምህርቷንም ፡ ትታ ፡ ስለባለገች ፡
ደሟንም ፡ ጠጣሁት ፡ እሷም ፡ ታረደች ።
እናቷም ፡ መለሰች ፡ እንዲህ ፡ እያለች ፡
እንዲህ ፡ ያለ ፡ በደል ፡ በእውነት ፡ ከሠራች
ሙሉ ፡ ፈቃዴ ፡ ነው ፡ እንኳን ፡ ታረደች ፡
ጭራሽ ፡ ክጃታለሁ ፡ ልጄም ፡ አይደለች ።
ብላ ፡ ተናገረች ፡ እናቷ ፡ ተናዳ ፡
ባንድ ፡ በኩል ፡ ደግሞ ፡ አልችል ፡ ብሏት ፡ ሆዷ
ታለቅስ ፡ ነበረ ፡ ገብታ ፡ ወደ ፡ ጓዳ ።
እናትና ፡ አባቷ ፡ ተነሥተው ፡ ወዲያው ፡
ግስጋሴ ፡ ያዙ ፡ ወደቤታቸው ፡
ወዲያው ፡ ከመንገዱ ፡ በደህና ፡ ደርሰው ፡
ከደጃዝማቻቸው ፡ ጋር ፡ ተገናኝተው ፡
ይጠይቁት ፡ ጀመር ፡ ስለአደራቸው ።
ደጃዝማቹም ፡ ደግሞ ፡ እንደለመደ ፡
ይዋሽ ፡ ነበረ ፡ እየጐማመደ ።
የርስዎ ፡ ልጅማ ፡ የሠራችው ፡ ሥራ ፡
ብተወው ፡ ይሻላል ፡ ጭራሽ ፡ ባይወራ ፡
አዳርዋ ፡ ውሎዋ ፡ ከጐረምሶች ፡ ጋራ ።
ሸርሙጥነት ፡ ይዛ ፡ ቀረና ፡ መማርዋ ፡

ትልቅ ፡ ሰው ፡ ስትሰድብ ፡ ደግሞ ፡ አለማፈርዋ ።
እኔ ፡ እንኳ ፡ እራሴ ፡ ቀ፡ቤአት ፡ ስታይ ፡
ትሰድበኝ ፡ ነበረ ፡ እንደ ፡ አንድ ፡ አገልጋይ ።
አለና ፡ ቢነግረው ፡ ላባቷ ፡ በውሸት ፡
ጭራሹን ፡ ሆነበት ፡ በንዴት ፡ ላይ ፡ ንዴት ።
ወዲያውም ፡ ሲገባኙ ፡ ግቢዎችን ፡ ሁሉ ፡
ያስቀሰችበት ፡ ያች ፡ ልጅ ፡ በሙሉ ፡
በጣም ፡ የሚያስደንቅ ፡ ስለ ፡ አበቃቀሉ ።
በመኖሪያ ፡ ቤትዋ ፡ ከግድግዳው ፡ ስር ፡
በብዙ ፡ ቀጤማ ፡ አብቅሎ ፡ ነበር ።
እናትና ፡ አባቷ ፡ ወዲያው ፡ እሱን ፡ አይተው ፡
እየተገረሙ ፡ በጣም ፡ ተመልክተው ፡
ደጃዝማቻቸውን ፡ ወዲያው ፡ አስጠርተው ፡
ይጠይቁት ፡ ጀመር ፡ በብርቱ ፡ አጥርተው ፡
ደጃዝማቹም ፡ ደግሞ ፡ እንደዚህ ፡ አላቸው ።
ልጅቷ ፡ ዘወትር ፡ ማታና ፡ ጠዋት ፡
አረቄና ፡ ጠጁን ፡ ስታፈስበት ፡
ቀጤማ ፡ አበቀለ ፡ ይኸውም ፡ መሬት ።
እናትና ፡ አባቷም ፡ እየተናደዱ ፡
ብለው ፡ አዘዙና ፡ በሉ ፡ አሁን ፡ እጨዱ ፡
እሱን ፡ አለፉና ፡ ወደሌላ ፡ ሄዱ ፡
ደግሞ ፡ እንደ ፡ ታዘዙ ፡ አሽከሮቹ ፡ሲያጭዱ ፡
መልሶ ፡ በቀለ ፡ ከስሩ ፡ ሳይሄዱ ፡
እናትና ፡ አባቷም ፡ ምን ፡ ይባላል ፡ ጉዱ ፡
በሉ ፡ ድገሙና ፡ አሁንም ፡ እጨዱ ፡
ብለው ፡ አዘዙና ፡ ወዴትም ፡ ሳይሄዱ ፡
እዚያው ፡ አጠገቡ ፡ ቆመው ፡ አሳጨዱ ፡
አሁንም ፡ መልሶ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ልማዱ ፡
በቀለ ፡ ቀጤማው ፡ አላለቀም ፡ ጉዱ ።

እናትና ፡ አባቷም ፡ ገርሚቸው ፡ ነገሩ ፡
ንቀሉልን ፡ አሉ ፡ በጭራሽ ፡ ከሥሩ ።
ወዲያው ፡ አሽከሮቹ ፡ እንደታዘዙት ፡
ቆፍረው ፡ ከሥሩ ፡ ነቃቅለው ፡ ጣሉት ።
ብላ ፡ ስትናገር ፡ የገዛ ፡ ጉዷን ፡
እየገረማቸው ፡ እናት ፡ አባቷን ።
ጉዱ ፡ የራሳቸው ፡ መሆኑን ፡ አውቀው ፡
እንዳይናገሩም ፡ መቀጫ ፡ ፈርተው ፡
ያዳምጡ ፡ ነበር ፡ በጭራሽ ፡ ፈዘው ።
ወንድሚንም ፡ ደግሞ ፡ አላስችል ፡ ቢለው
የሆነበት ፡ ሥፍራ ፡ እንደዚህ ፡ ያለው ፡
እባክህ ፡ ንገረኝ ፡ ወዴት ፡ አገር ፡ ነው ።
ልጅቷም ፡ አለችው ፡ ይቅርታ ፡ ወንድም ፡
ውለታ ፡ አድርጌአለሁ ፡ ከዚህም ፡ ቀደም ።
አሁን ፡ ቶሎ ፡ ብለህ ፡ ያለግርግር ፡
በውሉ ፡ መሠረት ፡ መድብ ፡ ሽውን ፡ ብር ።
እሱም ፡ እሺ ፡ ብሎ ፡ ብሩን ፡ መደበና ፡
ያዳምጥ ፡ ጀመረ ፡ ምን ፡ ጉድ ፡ ነው ፡ አለና ።
ልጅቷም ፡ ቀጠለች ፡ እንዲህ ፡ እያለች ፡
ይህችም ፡ ቆንጆ ፡ ልጅ ፡ የተበደለች ፡
በበረሃ ፡ ስትሄድ ፡ እያለቀሰች ።
ጠፍታ ፡ ስትኰበልል ፡ በቆራጥነት ፡
አንዲት ፡ ልጅ ፡ አገረድ ፡ አግኝታ ፡ ድንገት ።
እባክሽ ፡ አንች ፡ ልጅ ፡ የምለምንሽን ፡
አውልቂና ፡ ስጭኝ ፡ የውስጥ ፡ ልብስሽን ።
ልጅቷም ፡ ሰጠቻት ፡ ቀሚሷን ፡ አውልቃ
በድንገት ፡ መጥፋቷን ፡ መኰብለሏን ፡ አውቃ ፡
ወዲያውም ፡ ሸኘቻት ፡ መንገድ ፡ አሳይታ ፡

እሷም ፡ ደስ ፡ ብሏት ፡ ቀሚስ ፡ በማግኘቷ ፡
የለበሰችውን ፡ ስትወጣ ፡ ከቤቷ ፡
ሐር ፡ ስለነበር ፡ ያሰፋው ፡ አባቷ ።
ያንን ፡ ሐር ፡ ቀሚስ ፡ አውልቃ ፡ ጠቅልላ ፡
ጉዞዋን ፡ ቀጠለች ፡ በትከሸዋ ፡ አዝላ ።
ስትሄድ ፡ ቆይታ ፡ ችጋር ፡ ቢይዛት ፡
ምንተ ፡ ማርያም ፡ ብላ ፡ ገባች ፡ ከንጉሥ ፡ ቤት ።
ንጉሡም ፡ አዩና ፡ ቆማ ፡ ስትለምን ፡
ቶሎ ፡ ስጡአት ፡ አሉ ፡ መብል ፡ ምናምን ።
ወዲያውም ፡ አንዲቷ ፡ የንጉሡ ፡ ገረድ ፡
እንጀራ ፡ ልትሰጣት ፡ ይዛ ፡ ስትሄድ ።
አንችስ ፡ መላክ ፡ እንጂ ፡ ሰውስ ፡ አይደለሽም
እንደለማኝ ፡ ምግብ ፡ ፍጹም ፡ አልሰጥሽም ።
ብላ ፡ ተመለሰች ፡ እህሉንም ፡ መልሳ ።
ለንጉሡ ፡ ነገረች ፡ ቃልዋን ፡ አለስልሣ ።
ያች ፡ የቆመች ፡ ልጅ ፡ ከዚህ ፡ ከኛ ፡ ደጅ ፡
ሰው ፡ አትመስለኝም ፡ መልአክ ፡ ነች ፡ እንጅ ።
ንጉሡም ፡ መለሱ ፡ ነይ ፡ ግቢ ፡ በያት ፡
ምን ፡ ሰው ፡ እንደሆነች ፡ አጥብቄ ፡ ልያት ።
ገረዷም ፡ አለቻት ፡ ንጉሥ ፡ ይጠሩሻል ፡
በተቻለ ፡ ፍጥነት ፡ ነይ ፡ ግቢ ፡ ይሉሻል ።
እሷም ፡ ሄደችና ፡ ወደ ፡ ንጉሡ ፡ ፊት ፡
ይጠይቋት ፡ ጀመር ፡ እንዲህ ፡ በማለት ።
ያፈራ ፡ ብርቱካን ፡ ይመስላል ፡ ጉንጭሽ ፡
ደግሞም ፡ ሰውነትሽ ፡ ዓይንና ፡ ጥርስሽ ፡
የመልክሽ ፡ ቁንጅና ፡ ከነቅላትሽ ፡
የትስ ፡ ትሄጃለሽ ፡ ከየትስ ፡ መጣሽ ፡
እባክሽ ፡ ንገሪኝ ፡ እናት ፡ አባትሽ ፡

በሕይወት ፡ እያሉ ፡ እንዴት ፡ ለቀቁሽ ።
ልጅቷም ፡ መለሰች ፡ ውሀ ፡ ጥም ፡ ይዘኛል ፡
ሰውነቴን ፡ ደግሞ ፡ ድካም ፡ ተሰምቶኛል ፡
እንደዚሁም ፡ እራብ ፡ በጣም ፡ በዝቶብኛል ፡
መናገር ፡ አልቻልኩም ፡ በጭራሽ ፡ ደክሞኛል ።
ንጉሡም ፡ አዘዙ ፡ እንጀራ ፡ ስጧት ፡
ትብላ ፡ ትጠጣና ፡ እንድትጫወት ፡
ሥራም ፡ አታሠሩዋት ፡ ትቀመጥ ፡ እቤት ፡
ጭራሽ ፡ አትዘዙዋት ፡ አትናገሩዋት ።
እንደዚሁም ፡ ደግሞ ፡ የሳቸውም ፡ ልጅ ፡
በሽተኛ ፡ ነበር ፡ አይወጣም ፡ እደጅ ።
ጤንነቱን ፡ አጥቶ ፡ ሆኖ ፡ ሕመምተኛ ፡
ሰባት ፡ ዓመቱ ፡ ነው ፡ ባልጋ ፡ ላይ ፡ ከተኛ ።
ይህም ፡ በሽተኛ ፡ እንጀራ ፡ ሲበላ ፡
አይውጥም ፡ ነበረ ፡ ካንድ ፡ ጉርሻ ፡ ሌላ ።
ደግሞ ፡ ይህን ፡ ምግቡን ፡ የምትሠራለት ፡
ገረድ ፡ ነበረችው ፡ ልጅነት ፡ ያላት ።
ከዕለታት ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ድስት ፡ ስትሠራ ፡
ድስቱን ፡ እንደጣደች ፡ ገና ፡ ስታቁላላ ።
ሎጋው ፡ ሽበ ፡ እያለ ፡ ሠርገኛ ፡ ሲሄድ ፡
ልታዳምጥ ፡ ሄዳ ፡ ቆማ ፡ ከመንገድ ።
ወዲያውም ፡ ያች ፡ ልጅ ፡ ከቤት ፡ ተቀምጣ
ሲቃጠል ፡ ብታየው ፡ አሮ ፡ እየተንጣጣ ።
ድስቱን ፡ ሠራችና ፡ እንደሚገባው ፡
አውጥታ ፡ አስቀመጠች ፡ እዚያው ፡ እቦታው
ሠርገኞቹም ፡ ሄደው ፡ ሲጨልም ፡ ጊዜው ፡
መጣች ፡ ገረዲቷ ፡ ድስቱን ፡ አስታውሳው ፡
ወጡንም ፡ ተሠርቶ ፡ ስላገኘችው ፡

ብላ ፡ ጠየቀቻት ፡ ማነው ፡ የሠራው ።
ልጅቷም ፡ መለሰች ፡ እኔ ፡ ነኝ ፡ እቴ ፡ ሆይ፡
ይቅርታ፡አድርጊልኝ፡አጥፍቼ፡ይሆን፡ወይ ።
ገረዲም ፡ መለሰች ፡ እንኳን ፡ የሠራሽው ፡
በደንብ ፡ ከሠራሽ ፡ በስሎ ፡ ካወጣሽው ።
ወዲያው ፡ ደረሰና ፡ የምግብ ፡ ሰዓት ፡
ይኸ ፡ ሕመምተኛ ፡ ስጡኝ ፡ አለ ፡ እራት ።
እራቱም ፡ ቀረበ ፡ እንደተለመደው ፡
አንድ ፡ ጊዜ ፡ ጐርሶ ፡ ወጡንም ፡ወደደው ።
አለና ፡ ጠየቀ ፡ ዛሬ ፡ ይህን ፡ ወጥ ፡
የሠራችልኝ ፡ ሴት ፡ የትኛዋ ፡ ናት ፡
ገረዲም ፡ መለሰች ፡ ያጠፋች ፡ መስሏት ፡
ይች ፡ ልጅ ፡ ነበረች ፡ እኔ ፡ ሳላያት ፡
እሱም ፡ ጥሪያት ፡ አለ ፡ ቶሎ ፡ በፍጥነት ፡
እስዋም ፡ ትጠሪያለሽ ፡ ብላ ፡ ብትላት ፡
በጣም ፡ ደነገጠች ፡ ለቁጣ ፡ መስሎአት ፡
ልጁም ፡ እንዲህ ፡ ብሎ ፡ እሷን ፡ ጠየቃት
የሠራሽው ፡ ዛሬ ፡ አንቺ ፡ ነሽ ፡ ወይ ፡ ድስት
እስዋም ፡አዎን ፡አለች ፡ ሆዷ ፡ ሲጨንቃት
ሊቆጣኝ ፡ ነው ፡ ብላ ፡ ወድቃ ፡ በፍራት ።
እሱም ፡ በነገሩ ፡ እየተገረመ ፡
በልቶ፡ የማያውቀውን፡ሸራሽ ፡ ከታመመ።
አንድ ፡ እንጀራ ፡በልቶ፡ ያውም ፡ሳይጠቅመው
እናቱን ፡ ጠራና ፡ እንዲህ ፡ አላቸው ፡
ይገርማል ፡ ይደንቃል ፡ የዛሬው ፡ ጉድ ፡ ነው ፡
አንድ ፡ እንጀራ ፡ በላሁ ፡ ምሕረት ፡ ላገኝ፡ነው ።
ከዛሬም ፡ ጀምሮ ፡ የምበላውን ፡
የምታሰናዳ ፡ ይች ፡ ልጅ ፡ ትሁን ፡

እኔ ፡ አልፈልጋትም ፡ የፊተኛዋን ።
እናትና ፡ አባቱ ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ አላቸው ፡
ምግቡን ፡ እንድትሠራ ፡ ሆነ ፡ ፈቃዳቸው ፡
እስዋም ፡ እየሠራች ፡ ስትመግበው ፡
ልክ ፡ በሳምንቱ ፡ ሆነ ፡ ደህና ፡ ሰው ።
በአሥራ ፡ አምስተኛው ፡ ቀን ፡ ሆኖ ፡ በፈረስ ፡
ሄዶ ፡ ተመለሰ ፡ ብዙ ፡ አገር ፡ ድረስ ።
እንዲሁም ፡ሲሆነው ፡አንድ ፡ ወር ፡ ከሳምንት ፡
አምላክ ፡ ስለሰጠው ፡ ሙሉ ፡ ጤንነት ፡
አስበው ፡ አባቱ ፡ እንዲያገባ ፡ ሚስት ፡
አጥብቀው ፡ ጠየቁት ፡ እንዲይዝ ፡ ንብረት ።
እሱም ፡ ተናገረ ፡ ሚስት ፡ አግባ ፡ካሉኝ ፡
ያችን ፡ ቀላቢዬን ፡ በሕግ ፡ ይዳሩኝ ።
ለስዋ ፡ አላገባም ፡ እሞታለሁኝ ።
አባቱም ፡ መለሱ ፡ ጠይብ ፡ ትሁን ፡ ቡዳ ፡ የት
ብሎ ፡ ያውቃታል ፡
ዘርዋ ፡ ሳይታወቅ ፡ እንዴት ፡ ያገባታል ።
እስዋን ፡ አያገባም ፡ ሌላ ፡ እድረዋለሁ ፡
የመኳንንት ፡ ልጅ ፡ አጭቸለታለሁ ።
እሱም ፡ ተናገረ ፡ ሌላም ፡ አላገባ ፡
ስጡኝ፡ጠመንጃዬን፡ጭራሽ፡ውድማ ፡ልግባ ።
አባቱም ፡ መለሰ ፡ ከወደዳት ፡ ሆድህ ፡
አግብተህ ፡ ተቀመጥ ፡ ሁን ፡ እንደፈቃድህ ።
ወዲያውም ፡ ለእናቱ ፡ ነገሩን ፡ አጫውተው ፡
የማይቀር ፡ መሆኑን ፡ ገልጸው ፡ አስረድተው
ድግሱን ፡ ጀመሩ ፡ ሁሉን ፡ አዘጋጅተው ።
እንደዚሁም ፡ ደግሞ ፡ ድግሱ ፡ ሲደርስ ፡
በልኳ ፡ አሰፍተው ፡ የሐር ፡ ቀሚስ ፡

ኩታም ፡ አሠሩና ፡ ሰጥዋት ፡ እንድትለብስ ።
ሠርጉም ፡ ጥሩ ፡ ነበር ፡ ከልክ ፡ የተረፈ ፡
ያለቅጥ ፡ ያማረ ፡ ከመጠን ፡ ያለፈ ።
የሠርጋቸውም ፡ ቀን ፡ ሲቀረው ፡ ጥቂት ፡
አዘጋጅተውላት ፡ የሙሽራ ፡ ቤት ፡
አብረው ፡ የነበሩት ፡ ሆነው ፡ ባንድነት ፡
ልጆችም ፡ ነበሩ ፡ ካለችበት ፡ ቤት ፡
እስዋም ፡ ተናገረች ፡ እንዲህ ፡ በማለት ።

እንግዲህ ፡ አደራ ፡ በሰማይ ፡ በምድር ፡
አትናገሩብኝ ፡ ይኸንን ፡ ነገር ።
ብላ ፡ ወዲያውኑ ፡ ተናግራ ፡ ይህን ፡
አባቷ ፡ ልጅ ፡ ሁና ፡ ያሰፋላትን ፡
በወርቅ ፡ የነደደ ፡ ሐር ፡ ቀሚሷን ።
ይዛ ፡ ነበረና ፡ በጨርቅ ፡ ጠቅልላ ፡
አውጥታ ፡ ለበሰች ፡ ይግረማቸው ፡ ብላ ።
ተሞሸረችና ፡ ብቅ ፡ ብትል ፡ ለብሳ ፡
ቤት ፡ የተቃጠለ ፡ እሳት ፡ የተነሣ ።
ይኸ ፡ ሐር ፤ ቀሚስ ፡ ከቀላቷ ፡ ጋራ ፡
አስመሰለው ፡ ቤቱን ፡ ኤሌትሪክ ፡ የበራ ።
ይገረም ፡ ነበረ ፡ በመላው ፡ ፍጥረት ፡
እንደዚህ ፡ ያማረች ፡ የሆነች ፡ ውበት ።
አላየንም ፡ እኛ ፡ ከቶ ፡ ባለም ፡ ላይ ፡
ቀላቷ ፡ የሚያበራ ፡ እንደ ፡ ቀን ፡ ፀሐይ ።
እያሉ ፡ ያስቡ ፡ ነበር ፡ በልባቸው ፡
የዚች ፡ የልጅ ፡ ፍጥረት ፡ እየገረማቸው ።
በታላቅ ፡ ደስታ ፡ ሠርጉም ፡ አለፈና ፡
ወንድ ፡ ልጅ ፡ ወለደች ፡ ዓመት ፡ ቆየችና ።
ደግሞ ፡ ቆየችና ፡ አንድ ፡ ሁለት ፡ ዓመት ፡

አሁንም ፡ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ወለደችለት ፡
በጣም ፡ የተዋበ ፡ የቆነጀ ፡ ውበት ።
ወዲያው ፡ ቆየችና ፡ እናትና ፡ አባቴን ፡
እባክህ ፡ አሳየኝ ፡ እንሂድ ፡ አብረን ፡
ብላ ፡ ጠየቀችው ፡ በማስተዛዘን ።
እሱ ፡ መለሰላት ፡ ከሆዱ ፡ በውነት ፡
እሺ ፡ ምን ፡ ቸገረኝ ፡ እንሄዳለን ፡
እናትና ፡ አባቴ ፡ ከፈቀዱልን ።
ወዲያውም ፡ ለአባቱ ፡ ሄዶ ፡ ቢነግራቸው ፡
አይቻልም ፡ አሉት ፡ ጨከኖ ፡ ሆዳቸው ።
ቡዳ ፡ ትሁን ፡ ጠይብ ፡ ሳታውቅ ፡ አግብተህ ፡
ደግሞ አብረሃት ስትሄድ ብትቀርብኝ ወድቀህ
ብለው ፡ ከለከሉት ፡ ጨክነው ፡ አባቱ ፡
እሱም ፡ እያዘነ ፡ ይህን ፡ በመስማቱ ፡
ሄደና ፡ ነገራት ፡ ለመልካሟ ፡ ሚስቱ ፡
እሷም ፡ በጣም ፡ አዝና ፡ በኚሁ ፡ ባባቱ ።
ምን ፡ ይሻላል ፡ ታዲያ ፡ አለችው ፡ መልሳ
እያስተዛዘነች ፡ ቃሏን ፡ አለስልሳ ፡
ስለጠየቀችው ፡ መልሳ ፡ መልሳ ።
አንቺ ፡ በፊት ፡ ሂደሽ ፡ አባትሽን ፡ አይተሽ
አትቆይ ፡ በፍጥነት ፡ ቶሎ ፡ ተመለሽ ፡
አብረን ፡ እንሄዳለን ፡ ቆይተን ፡ ትንሽ ።
ብሎ ፡ ወታደሮች ፡ አሽከር ፡ አስከትሎ ፡
በጣም ፡ የሚያምነውን ፡ ደጃዝማች ፡ ጨምሮ።
የሚቀጥለውን ፡ አደራ ፡ ጭምር ፡
አደራ ፡ በሰማይ ፡ አደራ ፡ በምድር ፡
የልጆቼንና ፡ የሚስቴን ፡ ነገር ።
አደራዬን ፡ ሁሉ ፡ ባንተ ፡ ላይ ፡ ጥያለሁ ፡

እንደ ፡ መድኃኔ ፡ ዓለም ፡ አንተን፡አምኛለሁ ፡፡
ብሎ ፡ ለመነና ፡ አጥብቆ ፡ በብርቱ ፡
ሚስቱን ፡ ተሰናብቶ ፡ ቀረ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡፡
ብላ ፡ ስትናገር ፡ የራሷን ፡ በራሷ ፡
እሷም ፡ በገዛ ፡ አፏ ፡ በገዛ ፡ ምላሷ ፡፡
ባሏም ፡ ነበረና ፡ እፊቷ ፡ ተቀምጦ ፡
ከል ፡ እንደለበሰ ፡ ባዘን ፡ ተጨብጦ ፡
ይህንን ፡ ንግግር ፡ ሲሰማ ፡ ደንግጦ ፡፡
አለና ፡ ጠየቀ ፡ ታሪኳ ፡ ይገርማል ፡
ከሆነስ ፡ ሆነና ፡ ስሟ ፡ ማን ፡ ይባላል ? ፡፡
ልጅቷም ፡ መለሰች ፡ ወንድም ፡ ይቅርታህን ፡
አስቀምጥ ፡ አውጥተህ ፡ አሁን፡ሺህ ፡ ብርህን ፡
ወደፊትም ፡ ደግሞ ፡ ይህን ፡ ጥያቄህን ፡
እንዳታቀርብልኝ ፡ ሙሉ ፡ ይቅርታህን ፡
እለምንሃለሁ ፡ ወንድም ፡ አደራህን ፡፡
ይህንን ፡ ተናግራ ፡ ወዲያው ፡ ቀጠለች ፡
የሚቀጥለውን ፡ እንዲህ ፡ እያለች ፡፡
እሷም ፡ ስትሄድ ፡ ውላ ፡ ታጅባ ፡ ባሽከር ፡
ቀኑ ፡ ስለመሸ ፡ ብለው ፡ እንደር ፡
ድንኳን ፡ ተከሉና ፡ እልም ፡ ባለ ፡ ዱር ፡
ዙሪያውን ፡ ዘብ ፡ ቆሞ ፡ ብዙ ፡ ወታደር ፡፡
አልጋው ፡ ተነጥፎላት ፡ በድንኳኑ፡ውስጥ ፡
ልጆቿን ፡ ታቅፋ ፡ ተኝታ ፡ ጥቂት ፡
ደጃዝማቹ ፡ ገብቶ ፡ እንደዚህ ፡ አላት ፡፡
ያሉትን ፡ አይነሳ ፡ መቸም ፡ እግዚአብሔር ፡
እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ሳስብሽ ፡ ስኖር ፡
አገናኘን ፡ ዘሬ ፡ ወይ ፡ ያምላክ ፡ ነገር ፡
እንግዴህ ፡ እኅቴ ፡ አብረን ፡ እንደር ፡

ልጆችሽ ፡ ይውረዱ ፡ ይተኙ ፡ ከምድር ፡
እንተኛ ፡ አንቺና ፡ እኔ ፡ በመፈቃቀር ።
እሷም ፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ በብዙ ፡ ደንግጣ ፡
ካንተ ፡ ጋር ፡ አልተኛም ፡ ነፍሴ ፡ ብትወጣ ።
ባሌም ፡ አንተን ፡ አምኖ ፡ አደራ ፡ ሲልህ ፡
አዝናለሁ ፡ በውነቱ ፡ በመዘንጋትህ ፡
እንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ በመናገርህ ።
እሱም ፡ መለሰላት ፡ እንተኛ ፡ ይልቁን ፡
ልጅሽን ፡ አርደዋለሁ ፡ ይህንን ፡ ትልቁን ።
ሆድህ ፡ ከጨከነ ፡ እረደው ፡ እፊቴ ፡
ካንተ ፡ ጋር ፡ አልተኛም ፡ ሳለሁ ፡ በሕይወቴ ፡
ጥንትም ፡ እንደዚሁ ፡ በሕፃንነቴ ፡
ስለይ ፡ ጨክኜ ፡ ከእናቴ ፡ ካባቴ ፡
በዚሁ ፡ ነገር ፡ ነው ፡ ስወጣ ፡ ከቤቴ ።
እሱም ፡ ጨከነና ፡ እምቢ ፡ በማለቷ ፡
ልጅዋን ፡ አረደባት ፡ ወስዶ ፡ ከደረቷ ፡
ደግሞ ፡ እሬሳውን ፡ ዘረጋው ፡ እፊቷ ።
ስታለቅስ ፡ አድራ ፡ ሲነጋ ፡ ሌሊቱ ፡
ጉዞዋቸውን ፡ ያዙ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ትላንቱ ።
ሲሄዱ ፡ ዋሉና ፡ ስለመሸ ፡ ቀኑ ፡
እንደር ፡ አሉና ፡ ድንኳኑን ፡ ተከሉ ።
ወዲያው ፡ ሰዓት ፡ ሲደርስ ፡ ጊዜ ፡ የመኝታ ፡
ኣላት ፡ እንተኛ ፡ በፈጠረሽ ፡ ጌታ ።
ይህንን ፡ ስትሰማ ፡ እንዲህ ፡ አለችው ፡
ከኔ ፡ ጋር ፡ መኝታ ፡ ፍጹም ፡ ዘበት ፡ ነው ፡
ልብህም ፡ ማሰቡ ፡ በውነት ፡ ጨካኝ ፡ ነው ።
እሱም ፡ መለሰና ፡ እንደዚህ ፡ አላት ፡
በጭካኔ ፡ ሆዱ ፡ እያስፈራራት ።

ትናንት ፡ አረድኩብሽ ፡ ትልቁን ፡ ልጅሽን ፡
ዛሬ ፡ ልደግመው ፡ ነው ፡ ደግሞ ፡ ትንሹን ።
እሷም ፡ ተናገረች ፡ እንደፈቀደህ ፡
ካልሳሳህ ፡ እረደው ፡ ከፀና ፡ ሆድህ ፡
ከኔ ፡ ጋር ፡ መኝታ ፡ አያስብ ፡ ልብህ ።
እስኪወጣ ፡ ነፍሴ ፡ አፈር ፡ እስክሆን ፡
ካንተ ፡ ጋር ፡ አልተኛም ፡ ከቶ ፡ ምን ፡ ቢሆን ።
ወንድሜ ፡ ልንገርህ ፡ የሆዴን ፡ በውነት ፡
በጭራሽ ፡ አታስብ ፡ ከኔ ፡ ለመኛት ፡
በሕይወቴ ፡ ሳለሁ ፡ ለመገናኘት ።
አንተ ፡ አብደህ ፡ እንደሆን ፡ አላበድኩም ፡ እኔ ፡
በጣም ፡ እፈራለሁ ፡ በሰማይ ፡ ኵነኔ ።
ይህንን ፡ ሲሰማ ፡ በጨከነ ፡ ሆዱ ፡
ልጅዋን ፡ አርዶ ፡ ጣለው ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ልማዱ ፡
ሌሊቱም ፡ ሲነጋ ፡ ተነሥተው ፡ ሲሄዱ ፡
ቀኑ ፡ ስለመሸ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ልማዱ ።
ተቀምጠው ፡ ሳለ ፡ ድንኳን ፡ አስተክለው ፡
ይጠይቃት ፡ ነበር ፡ እንደሚቀጥለው ።
ከትላንት ፡ ወዲያና ፡ ትላንትና ፡ ማታ ፡
ልጆችሽ ፡ ታረዱ ፡ ያለሐዘኔታ ፡
ዛሬ ፡ አብረን ፡ እንደር ፡ በፈጠረሽ ፡ ጌታ ፡
እሷም ፡ ተናገረች ፡ ከእኔ ፡ ጋር ፡ መኝታ ፡
ልብህ ፡ እንዳያስብ ፡ ትላንትና ፡ ማታ ፡
አጫውቼሐለሁ ፡ ሁሉን ፡ በዝግታ ፡
የሆዴን ፡ ዘርዝሬ ፡ ሳልቸኩል ፡ በርጋታ ።
ምን ፡ ያደርግልሀል ፡ በከንቱ ፡ ምኞት ፡
የሕልም ፡ እንጀራ ፡ ነው ፡ ከኔ ፡ ጋር ፡ መኛት ።
ለምን ፡ አይገባህም ፡ ሰው ፡ የሚነግርህ ፡

መልሰህ ፡ መልሰህ ፡ ትጠይቃለህ ፡
አልገባህ ፡ እንደሆን ፡ ደግሞ ፡ ልንገርህ ፡
ከእኔ ፡ ጋር ፡ ለመኖት ፡ አያስብ ፡ ልብህ ፡
ልጆቼን ፡ አርደሃል ፡ ደግሞ ፡ ምን ፡ ቀረህ ፡
አንተ ፡ በውነተኛው ፡ አረመኔ ፡ ነህ ፡
እንደዚያ ፡ ለምኖ ፡ አደራ ፡ ሲልህ ፡
ምን ፡ አደራ ፡ በላ ፡ ጨካኙ ፡ ሰው ፡ ነህ ፡
ከሰዎቹ ፡ ሁሉ ፡ አንተ ፡ ተመርጠህ ፡
ለዚሁ ፡ ነበር ፡ ወይ ፡ አደራ ፡ ያለህ ፡
ምንኛ ፡ ጨካኝ ፡ ነው ፡ ከቶ ፡ ልቦናህ ፡
እንደምን ፡ ቢጠና ፡ ቢጨክን ፡ ሆድህ ፡
ለእንዲህ ፡ ያለ ፡ ነገር ፡ ሰው ፡ ትገላለህ ።
እሱም ፡ መለሰላት ፡ ውድ ፡ እህቴ ፡ ሆይ ፡
እግዜር ፡ ቢኰንናት ፡ ነፍሴን ፡ በሰማይ ፡
ካንቺ ፡ ጋር ፡ መኝታ ፡ ጽድቅ ፡ አይደለም ፡ ወይ ።
ላጠፋሁት ፡ ሁሉ ፡ ንስሐ ፡ እገባለሁ ፡
ዛሬ ፡ ግን ፡ ካንቺ ፡ ጋር ፡ ላድር ፡ ቆርጫለሁ ፡
እምቢ ፡ ብትይኝም ፡ ላርድሽ ፡ ታጥቄአለሁ ።
ከእኔ ፡ ጋር ፡ በፍቅር ፡ አብረሽ ፡ ከምታድሪ ፡
ምረጭ ፡ ከነፍስሽ ፡ ታርደሽ ፡ ከምትቀሪ ።
በውነቱ ፡ ከመጣህ ፡ ጨክነህ ፡ በራሴ ፡
አብረን ፡ እናድራለን ፡ አይብስም ፡ ከነፍሴ ።
አደራ ፡ ከማጉደል ፡ እርኩስ ፡ ከመሆን ፡
ቢቀር ፡ ይሻል ፡ ነበር ፡ እንደኔ ፡ ቢሆን ።
የማይቀር ፡ ከሆነ ፡ ከቶ ፡ ያሰብከው ፡
የቆሙትን ፡ ዘበኞች ፡ ትእዛዝ ፡ ስጣቸው ፡
አማን ፡ ነው ፡ አገሩ ፡ ተኙ ፡ በላቸው ።
እሱም ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ እውነቷን ፡ መስሎት ፡

ዘቦቹን ፡ ሰብስቦ ፡ ሁሉን ፡ ባንድነት ፡
ይሰብካቸው ፡ ጀመር ፡ እንዲህ ፡ በማለት ።
ተኙ ፡ ሁላችሁም ፡ እንደ ፡ ፈቃዳችሁ ፡
አማን ፡ ነው ፡ አገሩ ፡ አያስብ ፡ ልባችሁ ፡
በጭራሽ ፡ አትፍሩ ፡ አይሥጋ ፡ ሆዳችሁ ።
እያለ ፡ ሲናገር ፡ ይኽ ፡ ደጃዝማች ፡
ልጅቷ ፡ ባንድ ፡ ወገን፡ጠፍታ ፡ አመለጠች ።
ወዲያው ፡ ተመልሶ ፡ ሊተኛ ፡ ቢመጣ ፡
ባዶ ፡ ድንኳን ፡ እንጅ፡በውስጡ፡ሰው፡አጣ ፡
ያለቅጥ ፡ ደንግጦ ፡ ቢገባ ፡ ቢወጣ ፡
ቢጨነቅ ፡ ቢፈልግ ፡ ቢነድ ፡ ቢቆጣ ፡
አንድ ፡ ጊዜ ፡ ሄዳ ፡ ከየት ፡ አገር ፡ ትምጣ ።
ዘቦቹን ፡ ጠራና ፡ እውነት ፡ አስመስሎ ፡
ይናገር ፡ ጀመረ ፡ እንዲህ ፡ አሳምሮ ።
አባቱ ፡ ሲቆጡት ፡ ሲመክሩት ፡ ጥንቱን ፡
ቡዳ ፡ ትሁን ፡ ጠይብ ፡ ሳታውቅ ፡ ዘሩዋን ፡
እንዴት ፡ ታገባለህ ፡ ሲሉት ፡ ዱሮውን ፡
እምቢ ፡ ብሎ ፡ አግብቶ ፡ በራሱ ፡ ሥልጣን ፡
ሽማግሌ ፡ ያለው ፡ አይቀር ፡ ምን ፡ ቢሆን ፡
ሁለቱን ፡ ልጆቿን ፡ በላች ፡ ሰሞኑን ፡
የምትበላው ፡ አጥታ ፡ ጠፋች ፡ ጭራሹን ፡
እንሂድ ፡ ተነሱ ፡ ወደ ፡ ቤታችን ፡
እንደዚሁ ፡ ገልጸን ፡ እንናገራለን ፡
ብሎ ፡ ሰበከና ፡ ጨረሰ ፡ ውሸቱን ፡
ጉዞአቸውን ፡ ያዙ ፡ ነቅለው ፡ ድንኳኑን ።
ሲጓዙ ፡ ሰንብተው ፡ ሲደርሱ ፡ ከቤት ፡
ለባሏ ፡ ነገረው ፡ እንዲህ ፡ በማለት ፡
ሐሰቱን ፡ በሙሉ ፡ አስመስሎ ፡ እውነት ፡

ለካስ ፡ ቡዳ ፡ ኖራ ፡ ያንተ ፣ ባለቤት ።
ሁለቱን ፡ ልጆቿን ፡ ሰሞኑን ፡ በላች ፡
ደግሞ ፡ በማግስቱ ፡ እራሷ ፡ ጠፋች ፡
እንደ ፡ ዱር ፡ አራዊት ፡ ከጫካ ፡ ገባች ።
ባሏም ፡ ይኸን ፡ ሰምቶ ፡ በጣም ፡ አዘነና ፡
ልብሱን ፡ ሁሉ ፡ አውልቆ ፡ ከል ፡ ነከረና ፡
በኀዘን ፡ ተጨበጠ ፡ እውነት ፡ ነው ፡ አለና ።
ምነው ፡ በቀረብኝ ፡ ካንች ፡ መጋባቴ ፡
እንደ ፡ ከለከሉኝ ፡ እናትና ፡ አባቴ ።
በቀረብኝ ፡ ኖሮ ፡ ዓይኔ ፡ ባላየሽ ፡
የሕይወቴ ፡ ጌታ ፡ አለኝታዬ ፡ ነሽ ።
ይገባኛል ፡ ማልቀስ ፡ ይገባኛል ፡ ማዘን ፡
አበባዋ ፡ ሚስቴ ፡ ሆንሽብኝ ፡ ሰቀቀን ፡
እምን ፡ በታ ፡ ገብተሽ ፡ ወዴት ፡ ወድቀሽ ፡ ይሆን ።
ይመጣል ፡ በሕልሜ ፡ ዓይንና ፡ ጥርስሽ ፡
ደግሞ ፡ ትሕትናሽ ፡ የቁም ፡ ነገርሽ ።
አይጠፋም ፡ ከሆዴ ፡ ከቶ ፡ ምን ፡ ቢሆን ፡
እስከ ፡ ዘለዓለሙ ፡ ያንች ፡ ሰቀቀን ።
ወይ ፡ እኔ ፡ ዘንድሮ ፡ ምነው ፡ በዛ ፡ ጉዴ ፡
አንጀቴ ፡ ነደደ ፡ ተቃጠለ ፡ ሆዴ ።
አወይ ፡ የአምላክ ፡ ቁጣ ፡ አወይ ፡ የእግዜር ፡ ቁጣ
ምነው ፡ በቀረብኝ ፡ ከቤቴ ፡ ሳትወጣ ፡
ልጆቹ ፡ ሳይሞቱ ፡ እሷንም ፡ ሳላጣ ።
እንደዚህ ፡ እያለ ፡ ሲጨነቅ ፡ በብዙ ፡
ቀይ ፡ የነበረው ፡ ልጅ ፡ ጥቁር ፡ ሆነ ፡ ወዙ ።
ወዲያውም ፡ ያች ፡ ልጅ ፡ ጠፍታ ፣ ስትሄድ ፡
አንድ ፡ ሽማግሌ ፡ ቆመው ፣ ከመንገድ ፡
እየተገረሙ ፡ በዚች ፡ በልጅ ፡ ጉድ ፡

ያደንቁ ፡ ነበረ ፡ እያሉ ፡ ወይጉድ ።
ያች ፡ ልጅ ፡ ቆንጆ ፡ ነች ፡ እንደ ፡ መላእክት
በልሜ ፡ ነው ፡ በውኔ ፡ አሁን ፡ የማያት ።
ወደኔ ፡ ብትመጣ ፡ እጅ ፡ ብትነሳኝ ፡
እንዴት ፡ ዋሉ ፡ ብላ ፡ ብታነጋግረኝ ።
ሰላምታ ፡ ብትሰጠኝ ፡ ተናግራ ፡ እንደሰው
ንብረቴን ፡ በሙሉ ፡ በወሰደችው ፡
እያሉ ፡ ሲያስቡ ፡ በልቦናቸው ፡
ልጅቷ ፡ ተጠጋች ፡ አጠገባቸው ፡
እጅ ፡ ነሳቻቸው ፡ ቀርባ ፡ እፊታቸው ።
እሳቸውም ፡ አሏት ፡ እንዴት ፡ ዋልሽ ፡ እኅቴ ፡
በልሜ ፡ ነው ፡ በውኔ ፡ የቆምሽው ፡ እፊቴ ፡
እባክሽ ፡ ንገሪኝ ፡ አንቺ ፡ ልጅ ፡ በሞቴ ፡
ከየት ፡ አገር ፡ መጣሽ ፡ አትደብቂኝ ፡
እባክሽ ፡ ንገሪኝ ፡ አታስጨንቂኝ ።
እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ስኖር ፡ ባለም ፡ ላይ ፡
እንዳንች ፡ ያለ ፡ ቆንጆ ፡ አለሁኝ ፡ ሳላይ ።
ከፀጉርሽ ፡ የሽንጥሽ ፡ ከዓይንሽ ፡ የጥርስሽ
ደግሞ ፡ ያካሄድሽ ፡ ያረማመድሽ ።
እንዲሁም ፡ ንገሪኝ ፡ የምታስቢውን ፡
እኔ ፡ እሰጥሻለሁ ፡ የምትፈልጊውን ፡
ልጅቷም ፡ መለሰች ፡ የምፈልገውን ፡
ከሰጡኝ ፡ በሙሉ ፡ ልቤ ፡ ያሰበውን ፡
ያውልቁና ፡ ይስጡኝ ፡ ሱሪና ፡ ኮትዎን ።
እኛም ፡ ሽማግሌ ፡ ገረማቸውና ፡
ሱሪና ፡ እጀጠባብ ፡ ከቤት ፡ አመጡና ፡
ያውልሽ ፡ ልጄ ፡ ሆይ ፡ ውሰጂው ፡ አሉና ፡
ሰጡዋት ፡ ለልጅቷ ፡ በጣም ፡ አዘኑና ፡

እሷም ፡ ተቀብላ ፡ በታላቅ ፡ ምሥጋና ፡
የሐር ፡ ቀሚሷን ፡ አወለቀችና ፡
እንደወንድ ፡ ሱሪ ፡ ኮት ፡ ለበሰችና ፡
ጉዞዋን ፡ ቀጠለች ፡ በታላቅ ፡ ጐዳና ።
ስትሄድ ፡ ቆይታ ፡ በዚያው ፡ በመንገድ ፡
አንድ ፡ ሰው ፡ አገኘች ፡ ዕቃ ፡ ሲነግድ ።
ብላ ፡ ጠየቀችው ፡ አሳድረኝ ፡ ዛሬ ፡
ዘመዶችም ፡ የሉኝ ፡ እሩቅ ፡ ነው ፡ አገሬ ፡
ስገሠግሥ ፡ መጣሁ ፡ እንደመራኝ ፡ እግሬ ፡
እንዳላጫውትህ ፡ ብዙ ፡ ነው ፡ ታምሬ ።
እሱም ፡ መለሰና ፡ እንደዚህ ፡ አላት ፡
ያውም ፡ እየማለ ፡ ከሆዱ ፡ በውነት ።
እዚህ ፡ ተቀምጬ ፡ የምነግደው ፡
ወድጄን ፡ አይደለም ፡ ተቸግሬ ፡ ነው ፡
ምሣዬ ፡ አንድ ፡ እንጀራ ፡ ራቴም ፡ ያው ፡ ነው ፡
ደግሞ ፡ እኔ ፡ ቤት ፡ አድረህ ፡ ምን ፡ ልትበላ ፡ ነው ።
ልጅቷም ፡ መለሰች ፡ ምንም ፡ አልፈልግ ፡
ተጠግቼ ፡ ልደር ፡ ከዚህ ፡ ከቤት ፡ ጥግ ።
እሱም ፡ ተናገረ ፡ ላንድ ፡ ቀን ፡ አዳር ፡
በል ፡ ጠጋ ፡ በልና ፡ ተኝተህ ፡ እደር ።
ወዲያውም ፡ ሲበላ ፡ አምጥቶ ፡ እራቱን ፡
ያንን ፡ አንድ ፡ እንጀራ ፡ በፊት ፡ ያለውን ፡
ቆረሰና ፡ ሰጣት ፡ ለእሷ ፡ ግማሹን ።
እዚያው ፡ አደሩና ፡ ሲነጋ ፡ ሌሊቱ ፡
ትሄዳለች ፡ ብሎ ፡ ሲአያት ፡ ባለቤቱ ።
ጭራሽ ፡ ጠየቀችው ፡ እንደዚህ ፡ ስትል ፤
እባክህ ፡ ጌታዬ ፡ ካንተ ፡ ጋር ፡ ልሁን ።
እሱም ፡ መለሰላት ፡ ምን ፡ ልትሠራልኝ ፡

ለእኔውም ፡ ለራሴ ፡ በቂ ፡ ንግድ ፡ የለኝ ፡
ዛሬን ፡ ባሳድርህ ፡ እንድታጸድቀኝ ።
ልጅቷም ፡ መለሰች ፡ ጌታዬ ፡ ግድ ፡ የለም ፡
ወይ ፡ ትከብር ፡ ይሆናል ፡ ሰው ፡ እንዳይሆን ፡
የለም ፡
አንተም ፡ አባቴ ፡ ነህ ፡ ልጅህ ፡ ነኝ ፡ እኔም ፡
ካለሁ ፡ በሕይወቴ ፡ ካንተ ፡ አልለይም ።
ሰውዬውም ፡ አላት ፡ ከእኔ ፡ ለ መኖር ።
ፈቃድህ ፡ ከሆነ ፡ እንሁን ፡ አብረን ፡
በል ፡ ተቀመጥና ፡ የሆነው ፡ ይሁን ፡
እንነግዳለን ፡ ገዝተን ፡ ምናምን ።
ብሎ ፡ በማለስለስ ፡ ስለነገራት ፡
እጅግ ፡ ያለመጥን ፡ በጣም ፡ ደስ ፡ አላት ፡
ይነግዱ ፡ ጀመር ፡ ሻይና ፡ ብስኩት ፡
ወዲያውም ፡ ሰንብተው ፡ ቆይተው ፡ ጥቂት ፡
ብዙ ፡ ትርፍ ፡ አገኙ ፡ በሀብት ፡ ላይ ፡ ሀብት ።
እንዲህ ፡ ሲነግዱ ፡ እስከ ፡ ዓመት ፡ ድረስ ፡
በሀብት ፡ በገንዘብ ፡ በለጡ ፡ ከንጉሥ ።
ልጅቷም ፡ አለችው ፡ እናሠራ ፡ ቤት ፡
ይኸን ፡ ሁሉ ፡ ገንዘብ ፡ የምንከትበት ፡
ድግሥ ፡ እንደግሥ ፡ ብዙ ፡ ብዙ ፡ ዓይነት ፡
ከግራና ፡ ከቀኝ ፡ እንጥራ ፡ መንግሥት ፡
እንድንተዋወቅ ፡ ብዙ ፡ መኳንንት ።
እሱም ፡ መለሰላት ፡ እሺ ፡ የእኔ ፡ ልጅ ፡
ብታስተዋውቀኝ ፡ ከብዙ ፡ ወዳጅ ፡
እንዴት ፡ እጠላለሁ ፡ እወዳለሁ ፡ እንጅ ።
ወዲያው ፡ ተደግሦ ፡ ቤት ፡ ሙሉ ፡ ድግሥ ፡
ከግራና ፡ ከቀኝ ፡ ተጠራ ፡ ንጉሥ ።
እነዚህ ፡ ንጉሦች ፡ ግራ ፡ ቀኝ ፡ ያሉት ፡

አንዱ ፡ የባሏ ፡ አባት ፡ አንዱ ፡ የሷ ፡ አባት
ተጠርተው ፡ ሲመጡ ፡ ከዚያ ፡ ከሰው ፡ ቤት ፡
አብረውም ፡ ነበሩ ፡ ብዙ ፡ መኳንንት ፡
ደጃዝማች ፡ ቀኛዝማች ፡ ብዙ ፡ ሠራዊት ፡
እንተኛሽ ፡ ያሏትም ፡ ጥንት ፡ አባቷ ፡ ቤት ፡
ቄሱም ፡ ደጃዝማቹም ፡ ነበሩ ፡ አንድነት ።
ደግሞ ፡ ልጆቿንም ፡ አርዶ ፡ የጣላቸው ፡
ተቀምጦ ፡ ነበር ፡ አንድነት ፡ አብሮዋቸው ፡
የመጡት ፡ ቦሙሉ ፡ እንደሚገባቸው
ተጋብዘው ፡ ሲያበቁ ፡ በየበኩላቸው ።
እንደዚህ ፡ አለችው ፡ ልጅቷም ፡ እሱን ፡
ከተጋበዙልን ፡ እንግዶቻችን ፡
እንግዲህ ፡ በላቸው ፡ ትንሽ ፡ አጫውቱን ።
እነሱም ፡ አናውቅም ፡ ቢሉህ ፡ ምናልባት ፡
በያይነቱ ፡ ያውቃል ፡ የእኔ ፡ ልጅ ፡ ተረት ።
ነገር ፡ ግን ፡ ሲጫወት ፡ እሱ ፡ ተረቱን ፡
የሚያቋርጠው ፡ ሰው ፡ ያንን ፡ ጨዋታውን
ሽህ ፡ ብር ፡ እንዲከፍል ፡ ያጠብቃል ፡ ውሉን ፡
ብለህ ፡ ንገራቸው ፡ ዘርዝረህ ፡ ሁሉን ።
እሱም ፡ እሺ ፡ ብሎ ፡ ሄዶ ፡ ነገራቸው ፡
እስኪ ፡ ትንሽ ፡ ተረት ፡ አጫውቱን ፡ አላቸው ።
እነሱም ፡ መለሱ ፡ አንተ ፡ አጫውተን ፡ እንጅ ፡
ካንተ ፡ በጣም ፡ እኛ ፡ እንሆናለን ፡ ልጅ ።
ጨዋታ ፡ የሚያውቀው ፡ የዱሮ ፡ ሰው ፡ ነው ፡
አሁንም ፡ እራስህ ፡ አጫውተን ፡ አንተው ።
እሱም ፡ ተናገረ ፡ እናንተ ፡ ስሙ ፡ እንጅ ፡
በያይነቱ ፡ ተረት ፡ ያውቃል ፡ የኔ ፡ ልጅ ።
ነገር ፡ ግን ፡ ሲተርት ፡ እሱ ፡ ሲጫወት ፡

የተናገረው ፡ ሰው ፡ ባንድ ፡ ምክንያት ፡
ሸህ፡ ብር ፡ ይቀጣዋል ፡ የለውም፡ ምሕረት።
በማለት ፡ ተናግሮ ፡ ልጅቷን ፡ ጠራና ፡
በል ፡ ተጫወት ፡ አላት ፡ በሩን ፡ አዘጋና ።
እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ሲኖሩ ፡ አንድነት ፡
ብሎ፡አልጠረጠረም፡ ከቶ፡ሴት፡ ልጅ፡ ናት።
ብላ ፡ ስትናገር ፡ ሰውየው ፡ ደንግጦ ፡
እንዲህ፡ሲል፡ጠየቃት፡ ዓይኖቹን፡አፍጥጦ።
ምነው ፡ ልጄ ፡ ዛሬ ፡ ምነው ፡ ምን ፡ ሆነህል
የሆነ ፡ ያልሆነ ፡ ያስቀባጥርሀል ።
ልጅቷም ፡ መለሰች ፡ አልቀባጥርም ፡
ነገሬም፡እውነት፡ ነው፡ ውሸት፡ አይደለም።
አሁንም ፡ ቆይ ፡ እዚህ ፡ ብላ ፡ ሄደችና ፡
ከመኝታ ፡ ቤቷ ፡ ቶሎ ፡ ገባችና ፡
እሱንም ፡ ጠራችው ፡ ቶሎ ፡ አለችና ።
ወዲያው ፡ ነገረችው ፡ እንደዚህ ፡ ስትል ፡
እኔ ፡ ያወራሁት ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ታምር ፡
የኔ ፡ የራሴ ፡ ነው ፡ የሰውም ፡ አይደል ፡
አንተም ፡ አትደንግጥ ፡ አይበልህም ፡ ቅር።
እኔም፡ሴት፡ነኝ፡እንጂ፡አይደለሁም፡ ወንድ ፡
ይህንንም ፡ ገንዘብ ፡ ለራስህ ፡ ውሰድ ፡
ያፈራነውንም ፡ አብረን ፡ ስንነግድ ፡
ጭራሽ፡ አልፈልግም፡ አንዱንም ፡ አልወስድ።
የመጡትም ፡ ሰዎች ፡ እዚህ ፡ እኛ ፡ ቤት ፡
አንዱም ፡ የባሌ ፡ አባት፡ አንዱ ፡ የኔ ፡ አባት፡
ቁጭ ፡ ያሉትም ፡ ሴቶች ፡ አንድነት ፡ ያሉት
አንዷም ፡ የባሌ፡ እናት ፡ አንዷም፡ የኔ ፡ እናት ።
አንደኛው ፡ ቄስ፡ ደግሞ ፡ ሻሽ ፡ የጠመጠመው ፡

አባቴ ፡ ቤት ፡ ሆኜ ፡ ልተኛ'ሽ ፡ ያለኝ ፡ ነው ፡
ይህ ፡ ቀይ ፡ ልጅ ፡ ደግሞ ፡ እኔን ፡ የሚመስለው ፡
የእናት ፡ የአባቴ ፡ ልጅ ፡ ታላቅ ፡ ወንድሜ ፡ ነው ፡
ይህም ፡ ከል ፡ ለብሶ ፡ የተቀመጠው ፡
የልጆቼ ፡ አባት ፡ ነው ፡ ያ ፡ የምወደው ፡
ደጃዝማቹ ፡ ደግሞ ፡ በስተቀኝ ፡ ያለው ፡
ሁለቱን ፡ ልጆቼን ፡ አርዶ ፡ የጣለው ፡
ደግሞ ፡ በስተግራ ፡ የተቀመጠው ፡
አባቴ ፡ ቤት ፡ ሆኜ ፡ ልተኛ'ሽ ፡ ያለው ፡
ሁለቱ ፡ ጨካኞች ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ።
አንተ ፡ ግን ፡ ቁምና ፡ እይ ፡ ጉዳቸውን ፡
የነዚህን ፡ ሰዎች ፡ መጨረሻውን ።
ብላ ፡ ሄደችና ፡ ካልጋዋ ፡ ትራስ ፡
ያንን ፡ ወርቀ ፡ ዘቦ ፡ የሐር ፡ ቀሚስ ።
ፁጉርዋን ፡ አበጥራ ፡ ለባበሰችና ፡
ወደ ፡ ሰዎቹጋ ፡ ወዲያው ፡ ሄደችና ፡
ትናገር ፡ ጀመረ ፡ እንዲህ ፡ አለችና ።
አባቴም ፡ አንተ ፡ ነህ ፤
እናቴም ፡ አንች ፡ ነሽ ።
ወንድሜም ፡ ይኸ ፡ ነው ፡
ቁሱም ፡ እኚህ ፡ ናቸው ።
እነዚህም ፡ ደግሞ ፡ የባሌ ፡ እናት ፡ አባት ፡
አማቶቼ ፡ ናቸው ።
ከል ፡ የለበሰውም ፡ ባሌ ፡ ነው ፡ ልጃቸው ፡
ይህ ፡ ደጃዝማች ፡ ደግሞ ፡ እንደዚያ ፡ ጨክኖ ፡
ልተኛ'ሽ ፡ ያለኝ ፡ ነው ፡ አባቴ ፡ ቤት ፡ ሆኖ ።
ደግሞ ፡ ይኸኛው ፡ ነው ፡ ልጆቼን ፡ ያረደ ፡
በማላውቀው ፡ አገር ፡ እኔን ፡ ያሰደደ ።

ብላ ፡ ስትናገር ፡ ወንድሟ ፡ ፎክሮ ፡
ቄሱን ፡ በጐራዴ ፡ ጣለው ፡ አሽከርክሮ ።
ያንንም ፡ ደጃዝማች ፡ ደገመው ፡ ወዲያው ፡
እንዳረረ ፡ ሆዱ ፡ እንደ ፡ ነደደው ።
አውራሪሱን ፡ መዞ ፡ ባሏ ፡ ተነሣና ፡
ጣለው ፡ ያን ፡ ደጃዝማች ፡ አንገቱን ፡ አለና ።
እናትና ፡ አባትም ፡ እያለቃቀሱ ፡
ይስሟት ፡ ጀመረ ፡ እየመላለሱ ።
እየተገረሙ ፡ ሁሉም ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡
ተመልሰው ፡ ሄዱ ፡ ወደአሉበት ፡ አገር ።
እስዋም ፡ ከባልዋ ፡ ጋር ፡ ሄዳ ፡ ወደቤትዋ ፡
ወንድ ፡ ልጅ ፡ ወለደች ፡ ደግሞ ፡ በአንድ ፡
ዓመትዋ ።
ደግሞ ፡ ከባልዋ ፡ ጋር ፡ በመፈቃቀር ፡
ሲኖሩ ፡ ቆይተው ፡ በመተባበር ።
እንደዚህ ፡ ቆይተው ፡ ኖረው ፡ ብዙ ፡ ዓመት ፡
ሞተች ፡ ያች ፡ ቆንጆ ፡ ታማ ፡ በድንገት ።
ይማራት ፡ በሰማይ ፡ እግዚአብሔር ፡ ነፍስዋን
በምድር ፡ አይገኝም ፡ የሚያህል ፡ እስዋን ።
ፍጹም ፡ ያሳዝናል ፡ የሠራችው ፡ ሁሉ ፡
በቃ ፡ ተፈጸመ ፡ ታሪኳ ፡ በሙሉ ።
ኤርትራም ፡ እንዲሁ ፡ ብዙ ፡ ዓይነት ፡ መከራ ፡
ያለ ፡ ኀዘኔታ ፡ ስትቀበል ፡ ኖራ ።
ይኸውና ፡ ዛሬ ፡ ገባች ፡ ከሐገርዋ ፡
ነፃነት ፡ ለበሰች ፡ ደመቀ ፡ ምግባርዋ ።

## ም ክ ር ።

በተስፋ ፡ ከጸኑ ፡ አምኖ ፡ በእግዚአብሔር ፡
ያሰቡት ፡ ነፃነት ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ አይቀር ።
በእግዚአብሔር ፡ ያመነ ፡ በተስፋው ፡ የጸና ፡
በሰማይ ፡ ይማራል ፡ እንኳን ፡ በምድርና ።
የሀገሬ ፡ ሰዎች ፡ ስሙኝ ፡ ልምከራችሁ ፡
ባዛዦችሁና ፡ በበላዮቻችሁ ፡
ፍጹም ፡ አታስገቡ ፡ ቅናት ፡ በልባችሁ ፡
በውነት ፡ ከሠራችሁ ፡ በተስፋ ፡ ጸንታችሁ ፡
ከነሱ ፡ ይበልጣል ፡ ወደፊት ፡ ክብራችሁ ።
እገሌ ፡ በለጠኝ ፡ ብሎ ፡ ከመቅናት ፡
በውነቱ ፡ ይሻላል ፡ ተመስገን ፡ ማለት ፡
ያለመወላወል ፡ በተስፋው ፡ መጽናት ።
ጥንት ፡ እበልጠው ፡ ነበር ፡ ዛሬ ፡ ቢበልጠኝ ።
በምን ፡ ምክንያት ፡ ነው ፡ እሱ ፡ የሚያዘኝ ።
እያሉ ፡ ዘወትር ፡ ከመቅናት ፡ በበላይ ፡
ይሻል ፡ ይመስለኛል ፡ መትጋት ፡ በሥራ ፡ ላይ ።
ሹመትና ፡ ማዕርግ ፡ ገንዘብና ፡ ወርቅ ፡
በመልካም ፡ ከሠሩ ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ አይርቅ ።
ከተጋን ፡ በሥራ ፡ እኛ ፡ ሁላችን ፡
ምን ፡ ጊዜም ፡ አናጣ ፡ እንደ ፡ እድላችን ፡
ካለልን ፡ ተፈሪ ፡ ደጉ ፡ ጌታችን ፡
የነፍሳችን ፡ አባት ፡ የሕይወታችን ፡
ከዚያ ፡ ከመከራ ፡ ከጭንቅ ፡ ያወጣን ፡
ዕድሜውን ፡ ያርዝመው ፡ ቸሩ ፡ አምላካችን ፡
እንደዚህ ፡ ተቀጣሁ ፡ ብሎ ፡ ከማዘን ፡
በብርቱ ፡ ማክበር ፡ ነው ፡ አጥብቆ ፡ ሕግን ።

በጣም ፡ ካከበሩ ፡ ሥነ ፡ ሥርዓትን ፡
ሊያገኘው፡አይችልም ፡ማንም፡ሰው፡ ቅጣትን።
በሥራ ፡ ከተጉ ፡ ከተጠነቀቁ ፡
ሥነ ፡ ሥርዓትና ፡ ሕግን ፡ ከጠበቁ ፡
በደል ፡ እንደሌለ ፡ በፍጹም ፡ እወቁ ።
ነገር ፡ ግን ፡ አንድ ፡ አንዴም ፡ እግዚአብሔር
ሲቆጣ ፡
ያልታሰበ ፡ አደጋ ፡ በድንገት ፡ ቢያመጣ ።
እያጉረመረሙ ፡ ከማማረር ፡ ፈንታ ፡
ሁል ፡ ጊዜ ፡ ዘወትር ፡ በሳቅ ፡ በደስታ ፡
ተመስገን ፡ ብንለው ፡ ደጉ ፡ የኛ ፡ ጌታ ፡
ምሕረት ፡ ልማዱ ፡ነው ፡ ዘላለም ፡ይቅርታ ።
ከፍ ፡ ያለ ፡ ምሕረቱን ፡ የተለመደውን ፡
ይሰጠናልና ፡ የማይዛባውን ።
እናቅርብ ፡ ምስጋና ፡ በመደጋገም ፡
ለቸሩ ፡ ጌታችን ፡ ለመድኀኔ ፡ ዓለም ።
ይክበር ፡ ፈጣሪያችን ፡ በጣም ፡ እጅጉን ፡
በሥራው ፡ የተጋ ፡ ያመነ ፡ ጌታን ።
አያጣም ፡ ዘላለም ፡ ከፍተኛ ፡ ዋጋ ፡
ምን፡ ጊዜም ፡አትርቀው፡ የእግዚአብሔር ፡ጸጋ
ትመጣለታለች ፡ በነጋ ፡ በነጋ ፡
ያለበትን ፡ ስፍራ ፡ እራሷ ፡ ፈልጋ ።
ስለዚህ ፡ አደራ ፡ አንባቢዎች ፡ ሁሉ ፡
እንትጋ ፡ በሥራ ፡ ሁላችን ፡ በሙሉ ።
ንብ ፡ አይተህ ፡ ተገዛ ፡ እንደሚባለው ፡
እኛም ፡ ለንጉሣችን ፡ ለምንወደው ፡
ለኀይለ ፡ ሥላሴ ፡ ለድል ፡ አድራጊው ፡
በቅን ፡ እናገልግል ፡ እንደሚገባው ።
እንሥራ ፡ ጠንክረን ፡ ለውድ ፡ አገራችን ፡

ደግሞ ፡ እንተባበር ፡ አንድነት ፡ ሁላችን ፡
ሆዳችን ፡ ይራራ ፡ ለእናት ፡ ለአባታችን ፡
ለመላ ፡ ቤተ ፡ ሰብ ፡ ለዘመዶቻችን ።
አባትን ፡ አባባ ፡ እናትን ፡ እማዬ ፡
እኅትን ፡ አበባ ፡ ወንድምን ፡ ጋሺዬ ፡
አዛዥን ፡ ጌታዬ ፡ አያትን ፡ እምዬ ።
እያልን ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ በመተባበር ፡
እንኑር ፡ ዘላለም ፡ በመፈቃቀር ።
ዕድሜ ፡ ለግርማዊነታቸው ፡
ከነመላው ፡ ቤተ ፡ ሰባቸው ፡
እኔ ፡ ነኝ ፡ እሸቴ ፡ ቅን ፡ አገልጋያቸው ።

